# ማርክሲዝምና የቋንቋ ችግሮች


ከ-ጆሴፍ እስታሊን

ትርጉር፤-በደበበ ሰይፉ






መጀመሪያ እትም ፲፱፻፸ ዓ.ም

ሁለተኛ እትም ፲፱፻፸፭ ዓ.ም

ሦስተኛ እትም ፲፱፻፸፯ ዓ.ም

በሴንትራል ማተሚያ ቤት ታተመ።

ማውጫ፡፡

## ከአንባቢ

ስለ ቋንቋ ምንነትና መነሻ በርከት ያሉ ሰዎች የተለያዩ ሐሳቦች ሰንዝረዋል፡፡ አንዳንዶቹ ቋንቋ እግዚአብሔር ከሰው ልጆች ጋር አብሮ የፈጠረው ነው ሲሉ አንዳንዶቹ ደግሞ ቋንቋ ከሰው ጋር አብሮ የተፈጠረ ሳይሆን ሰው በአንባቢው ከሚሰማቸው ድምፆች አቀነባብሮ የያዘው ነው ይላሉ፡፡ እንዲሁም ሌሎቹ ቋንቋ ባጋጣሚ የተገኘ እንጂ የተፈጠረውም ያቀነባበረውም የለም ይላሉ

እነዚህን የመሰሉት ግምቶች የሚመነጩት ነገርን በተናጠል ከመመልከት ነው፡፡ ቋንቋ በቋንቋነቱ ብቻ ተመልክቶ ቋንቋ በተለይ ወገንንቱ ከየት እንደሆነ ሳያገናዝቡ የሚሰጠው መላ ምት ብዙም አያስኬድ፡፡ የቋንቋን ምንነትና ምንጭ ለማወቅ መነሻችን ዛሬ በቋንቋ ተገልጋይ የሆነውን ወገን ማንነትና ምንነት መረዳት ነው፡፡

እስካሁን መረጃና ባለን ዕውቀት መሠረት በቋንቋ ተገልጋይ የሆነ ወገን ማኅበረሰብ ነው፡፡ ማኅበረሰብም በቋንቋ ሲገለገል የደረሰበትን ወቅትና ምክንያት ፍሬደሪክ ኤንግልስ ሲያስረዳ እንዲህ ይላል፡፡

የጋራ መደጋገፍንና የጋራ ሥራን የሚጠይቁ ሁኔታዎችን ከፍ በማድረግ፤ እንዲሁም የዚህን የጋራ ሥራ ጥቅም ለእያንዳንዱ ለግለሰብ በማድረግ የተግባር እድገት የማኅበረሰብ አባሎችን አንድነት ለመሰብሰብ የግድ ረድቷል፡፡ ባጭሩ ሰዎች በተግባር ላይ እያሉ አንዱ ሌላውን አንድ ነገር ማለት እተገደደበት ደረጃ ላይ ደረሰ፡፡ የሁኔታው አስገዳጅነት የልሳን አባላትን አስገኘ፡፡

(የሰው ልጅንና) እንስሳትን ማወዳደር የቋንቋ ምንጩ ተግባርና የተግባር ሂደት ነው የሚለው ብቸኛ ትክክለኛ ማስረጃ መሆኑን ያረጋግጣል፡፡ እጅግ የዳበሩ (በአእምሮ) ናቸው የሚባሉት እንስሳት እንኳ ለመግባቢያ የሚያስፈልጋቸው ጥቂቱ የአባላተ ልሳናት ቅንጅት አይፈልጉም፡፡ በተፈጥሮ ውስጥ ማንኛውም እንስሳ ከሰው ጋር ለመነጋገር ባለመቻሉ ወይም የሰውን ንግግር ለመረዳት ባለመቻሉ ችግር አይሰማውም፡፡ (ማርክስና ኤንግልስ፤ ምርጥ ጽሑፎች፤ ቅጽ፤ 1 እና ገጽ 68)፡፡

እንግዲህ ከዚህ ጥቅስ እንደምንረዳው ቋንቋ ተግባር ያስገኘው ማኅበረሰብ መግባቢያ ዘዴ ነው፡፡ በተግባር ውጤትነቱም እንደ የማኅበረሰቡ የተግባር ስፋትና ጥበት ይሰፋል፤ ይጠባል፡፡ ከማኅበረሰብ ተግባር ውጭ ቋንቋ ያስገኘ፤ ከተገኘም በኋላ ቢሆን የገዛና የሚገዛ ሌላ ኃይል የለም፡፡ የሰው ልጅ ለመኖር በሚያደርገው ትግል ዕውቀቱ እየዳበረ የደረሰበት ደረጃ ባስቻለው መጠን ተፈጥሮን የመቆጣጠር ተግባር የሚያከናውነው እሱው ብቻ ስለ ሆነ ቋንቋ የሰው ልጅ ብቻ መግባቢያ ዘዴ ነው፡፡

የሰው ልጅ በማኅበረሰብ ተሰብስቦ ለመኖር ባደረገው ትግል ከመደብ አልባው ጥንታዊ የጋርዮሽ ሥርዓት በኋላ በመደብ መከፈሉን፤ ከዚያም የባሪያ አሳዳሪን፤ የፊውዳልንና

የካፒታሊስትን ሥርዓት ማኅበሮች አልፎ መደብ የለሽ የኮሙኒስት ሥርዓት ማኅበርን እንደሚመሠርት የሳይንሳዊ ሶሻሊዝም ቀደምት አባቶች አስተምረዋል። እነዚህም ሥርዓተ ማኅበሮች ምንም እንኳ አንዱ ከሌላው የሚወለድ ቢሆንም ሌላው ማደግ ቀድሞት ባለው ማርጀትና መሞት ላይ የተመሠረተ መሆኑንም አስረድተዋል። በነዚህም የማኅበረሰብ የእድገት ደረጃዎች ሁሉ ቋንቋ ነበረ። ይኖራልም።

ቋንቋ የማኅበረሰብ ተግባር ያስገኘው የመግባቢያ ዘዴ ነው ከተባለና ከሁሉም የማኅበረሰብ የእድገት ደረጃዎች ውስጥ ያለና የሚኖር ነው ካልን ከእነዚህ የማኅበረሰብ የእድገት ደረጃዎች ጋር ያለው ግንኙነት እንዴት ነው የሚለው ጥያቄ ይነሳል። የችኩል መልሣችንም «ያው ቋንቋውም እንደ የሥርዓተ ማኅበሩ አዲስ ይሆናል» የሚል ይሆናል። ነገር ግን ተተርጉሞ እቀረበው እዚህ መጽሐፍ ውስጥ ጆሴፍ ስታሊን የሚሰጠው መልስ ከዚህ የተለየ ነው። ይህ ስታሊን የሰጠው መልስ ምን እንደሆነ መጽሐፉን በጥሞና አንብቦ ለመረዳት ይቻላል።

ጆሴፍ ስታሊን የሚሰጠውን መልስ ለመረዳት እንዲያግዝ ግን ስታሊን በተለይም ደግሞ የቋንቋ ሊቃውንት ቋንቋ የሚሉት ምንን እንደሆነ መገንዘብ ያስፈልጋል። ቋንቋ የሚባለው ምኑ ነው? ቃላቱ? ድምፁ? ወይስ ሌላ? ቋንቋ የሚባለው ድምፁ ብቻ አይደለም። ቋንቋ የሚባለው በመዝገበ ቃላት ውስጥ የምናገኘው የቃላት ክምችት አይደለም። ቋንቋ የሚባለው፣ ቀለል ባለ አገላለጽ፣ ድምጾች ሥርዐት ባለው መንገድ ተጋጥመውና ቃላትን ሁነው፣ ቃላትም እርስ በርሳቸው ሐሳብን ለመግለጽ በሚችሉበት ዘዴ ተቀናጅተው እሚገኙበት ማኅበረሰቡ በልማድ የሚከተለው ሥርዓት ነው። በመድበለ ቃላቱ ውስጥ ያሉ መሠረታዊ ያልሆኑ ቃላት በየጊዜው ይወለዳሉ፣ ይሞታሉ። የቋንቋ ሕይወት የሆኑት ድምጾችና እነሱም ተቀነባብረው ሀሳብ ለመስጠት የሚችሉበት ሥርዓት ግን የሚያሳየው ለውጥ እጅግ ዘገምተኛና ለዘብተኛ ነው።

ይህ የጆሴፍ ስታሊን መጽሐፍ የቋንቋንና የማኅበረሰብን የእድገት ደረጃዎች (የልዩ ልዩ ሥርዓተ ማኅበሮችን) ግንኙነት ለመረዳት ብቻ ሳይሆን ብዙ ቋንቋዎች በሚነገሩባቸው አገሮችና በዓለም አቀፍም ደረጃ ከኅብረተሰባዊነት ሥርዓተ ማኅበር መደርጀት በፊትና በኋላ ስለሚታዩት የቋንቋዎች ሁኔታም ለመገንዘብ ይረዳል። ለምሳሌ በዚህ አንጻር በኢትዮጵያ ውስጥ ከየካቲት 1966 ወዲህ በርከት ያሉ የኢትዮጵያ ቋንቋዎች በመገናኛ ዘዴዎች መሰማታቸው እንግዳ ነገር ለሚመስላቸው፣ ስታሊን «......በመጀመሪያ ደረጃ፣ በእርግጥ የብሔረ ሰብ ጭቆና የሚወገድበት ጊዜ፣ ቀድሞ ይጨቆኑ የነበሩ ብሔረሰቦችንና ቋንቋዎችን ማደግና ማበብ...... ያመጣል» ይላል።

የዚህ መጽሐፍ ተርጓሚ በመግቢያው ላይ እንደገለጸው «መጽሐፉን ከቋንቋ ምሁራን ክበብ ውጪ ያሉ ሰዎችም ያሉ ሰዎችም እንዲጠቀሙበት ለማድረግ.....» ጥሯል። ይሁን እንጂ የቋንቋ ምሁራንም ሆኑ ሌሎች አንባቢያን እጅግ ቢያንስ <u>ኮሙኒስት ማኒፌስቶን</u> አስቀድመው ቢያነቡ መጽሐፉን በሚገባ ለመረዳት ያግዛቸዋል። በዚህ መጽሐፍ ውስጥ የተነሱትን ሀሳቦች ሰፋ ካለ ሁኔታ ጋር ለማገናዘብ ደግሞ የስታሊንን <u>ማርክሲዝምና የብሔር ጉዳይ፣</u> እንዲሁም የሌኒን <u>የብሔረሰቦች የራሳቸውን ዕድል በራሳቸው የመወሰን መብት</u> ማንበብ ይጠቅማል።

## መግቢያ፡፡

በሀገራችን የዘመናዊ ቋንቋ ጥናት ባህል አልዳበረም፡፡ አማርኛም በዚህ ባህል ውስጥ ላሉ ጽንሰ ሐሳቦች ማካተቻ እሚሆኑ ቃላት የሉትም፡፡ ይህን መጽሐፍ ለመተርጐም ስነሳም ያጋጠመኝ ዐቢይ ችግር ይኸው ነበር፡፡ መጽሐፉ ተነባቢነት እንዲኖረውና ከቋንቋ ምሁራን ክበው ውጪ ያሉ ሰዎችም እንዲጠቀሙበት ለማድረግ አንዳንድ ቃላት እንደ አዲስ አስገብቻለሁ፡፡ ከነዚህም ውስጥ ከበድ ይላሉ ያልኳቸውን በንባቡ ውስጥ በኮከብ ምልክት ከመጠቆሜና አምደ ቃላት አዘጋጅቼ የእንግሊዝኛ አቻቸውን ከመስጠቴም በላይ ላብራራቸውም ሞክሬአለሁ፡፡ በተጨማሪም የአማርኛው በቀላሉና በግልጽ መስማስ እጅግ አስፈላጊና ተቀዳሚ ጉዳይ በመሆኑ ከቀጥታ ቃል በቃል መስመር በመስመር ትርጉም እጅግ በመጠኑ ፈቀቅ ብዬአለሁ፡፡ በቃላትም በኩል ሲሆን ይህንኑ መንገድ ነው የተከተልሁ፡፡ ለምሳሌ Linguistics የሚለው የእግሊዝኛ ቃል «ሥነ ቋንቋ» በሚለው በደንብ እንደሚተረጐም ባውቅም «ቋንቋ» «የቋንቋ ጥናት» እያልኩ ያለፍኩበት ጊዜ አለ፡፡ የዚህም ምክንያቱ ለብዙ ሰው ይሄ መንገድ ተስማሚነት ይኖረዋል ብዬ ስላሰብኩና የከፋ የትርጉም ስብራት ያመጣል ብዬ ስላልገመትኩ ነው፡፡ የመጽሐፉን አርእስትም ቢሆን <u>ማርክሲዝምና የሥነ ቋንቋ ችግሮች</u> ሣይሆን <u>ማርክሲዝምና የቋንቋ ችግሮች</u> ማለቴ በዚህ ምክንያት ነው፡፡

ቋንቋ የመገናኛ መሣሪያ በመሆኑ ረገድ በየትምህርት ቤቶች ሆነ በግለሰቦች ለሚሠነዘሩ ጥያቄዎች ይህ የጆሴፍ እስታሊንን መልሶች የያዘ መጽሐፍ በጣም እንደሚጠቅም አይጠረጠርም፡፡ የቋንቋ መምህራንም መጽሐፉ ውስጥ ያሉ የውጭ ሀገር ምሣሌዎችን በሀገር ውስጥ ምሣሌዎች እየተኩ እንደሚገለገሉበት ተስፋ አደርጋለሁ፡፡

በመጽሐፉ ውስጥ ያሉ የዘመን አቆጣጠሮች በሙሉ የጐርጐሮሣውያን ናቸው፡፡

ተርጓሚው፡፡

## በሥነ ቋንቋ ውስጥ ማርክሲዝምን

## ስለሚመለከተው ጉዳይ

ወጣት ጓዶች በሥነ ቋንቋ ውስጥ ስላሉ ችግሮች በተለይም ማርክሲዝም በሥነ ቋንቋ ላይ ምን ምን ሀሣቦች እንዳሉት በጋዜጦች እንድገልጥ ጠይቀውኛል፡፡ የሥነ ቋንቋ አዋቂ አይደለሁም፡፡ በመሆኑም ጥያቄዎቻቸውን ሙሉ በሙሉ መመለስ አልችልም፡፡ ይሁንና ማርክሲዝም በሥነ ቋንቋ ውስጥ ሆነ በሌሎች ማኅበረሰባዊ ሳይንሶች ላይ ስላሉት ሀሣቦች ከሆነ፤ ይህ በቀጥታ የሚመለከተኝ ነገር ነውና እነሆ በጓዶች የተሠነዘሩ አንዳንድ ጥያቄዎችን እመልሣለሁ፡፡

ጥያቄ፤ ቋንቋ ኢኮኖሚያዊ መዋቅር ላይ ያለ ሉዓላዊ መዋቅር ነው መባሉ እውነት ነው?

መልስ፤ የለም፤ እውነት አይደለም፡፡

ኢኮኖሚያዊ መዋቅር አንድ ማኅበረሰብ ባንድ በተወሰነ የእድገት ደረጃው የሚያሣየው የኢኮኖሚ መልኩ ነው። ሉዓላዊ መዋቅር ማኅበረሰቡ ያለው የፖለቲካ፤ የሕግ፤ የሀይማኖት የኪነት፤ የፍልስፍና አተያዮችና ከኒሁ ጋር የሚቋጩ የፖለቲካ የሕግና የሌሎችም ተቋሞች ድምር ነው።

እያንዳንዱ ኢኮኖሚያዊ መዋቅር የራሱ የሆነ ሉዓላዊ መዋቅር አለው። የጉልታዊ ሥርዓት የኢኮኖሚያዊ መዋቅር የራሱ ሉዓላዊ መዋቅር፤ የራሱ የፖለቲካ የሕግና የሌሎችም አስተያዮች ከኒህም ጋር የሚቋጩ ተቋሞች አሉት። የከበርቴው ሥርዓትም እንዲሁ። ኢኮኖሚያዊ መዋቅሩ ቢለወጥ ወይ ቢጠፋ ይህንኑ ተከትሎ ሉዓላዊ መዋቅሩም ይለወጣል፤ ወይ ይጠፋል። ቀጥሎም ሌላ ኢኮኖሚያዊ መዋቅር ቢመሠረት ከዚሁ መዋቅር ጋር የሚቋጭ ሉዓላዊ መዋቅር ይፈጠራል።

ነገሩን እንዲህ ስናየው ቋንቋ ከሉዓላዊ መዋቅሩ እጅግ ይለያል። ለምሣሌ ያህል የሩስያን ቋንቋና የሩሲያን ማኅበረሰብ መውሰድ ይቻላል። ባለፉት ፴ ዓመታት የቀድሞው የከበርቴ ኢኮኖሚያዊ መዋቅር በሩስያ ጠፍቷል፤ አዲስ ኅብረተሰብዓዊ ኢኮኖሚያዊ መዋቅርም ተገንብቷል። በአንጻሩም በሥርዐተ ከበርቴው ኢኮኖሚያዊ መዋቅር ላይ በቅሎ የነበረው ሉዓላዊ መዋቅር ጠፍቷል። ቀድሞ የነበሩት የፖለቲካ፤ የሕግና ሌሎችም ተቋሞች በሌሎች በአዲስ ኅብረሰተባዊ ተቋሞች ተተክተዋል። ግና ይህ ሁሉ ሁኖ ሣለ የሩሲያ ቋንቋ መሠረታውያን ነገሮች ከጥቅምት አብዮት በፊት በነበሩት ሁኔታ ዛሬም አሉ።

መሆኑን በዚህ ጊዜ ሁሉ በሩስያ ቋንቋ ላይ የታየ ለውጥ ምንድን ነው? የሩስያ ቋንቋ እጅግም ባይሆን በቃላት በኩል ተለውጧል። ተለውጧልም ስንል ከአዲስ ኅብረተሰባዊ ምርት መፈጠር ከአዲስ መንግሥት መገኘት፤ ከአዲስ ኅብረተሰባዊ ባህል መስረጽ፤ ከአዲስ ኅብረተሰባዊ ግንኙነቶችና የሞራል መልኮች መታየት፤ በመጨረሻም ከቴክኖሎቺና ከሣይንስ እድገት ጋር በተያያዙ ምክንያቶች በዛ ባሉ አዳዲስ ቃላትና የአገላለጽ ዘዬዎች ተመልቷል ማለታችን ነው። አንዳንድ ቃላትና የአገላለጽ ዘዬዎች የቀድሞ ትርጉማቸውን ለውጠዋል። አዳዲስ ሀሣቦችን እንዲገልጹም ተደርገዋል። አንዳንድ ነባር ቃላትም ከሩሲያ ቋንቋ መድበለ ቃላት ወጥተዋል። ይሁንና የከበርቴው ኢኮኖሚያዊ መዋቅር ከጠፋ ወዲህም ቢሆን እንኳንስ የሩስያ ቋንቋ፤ የአንድ ቋንቋን መሠረታዊ መልክ በሚይዘው በነባርና መሠረታዊ የመድበለ ቃላቱ ክፍልና የሰዋሰው ሥርዓቱ ሊጠፋና በሌላ አዲስ ነባርና መሠረታዊ የመድበለ ቃላት ክፍልና የሰዋሰው ስርዓት ሊተካ ይቅርና፤ አንዳችም ከባድ ለውጥ ሣያሣይ እንደ ነበር ቆይቷል። የዘመናዊው የሩስያ ቋንቋ መሠረት በመሆንም ፀንቷል።

ሉዓላዊ መዋቅሩ የኢኮኖሚያዊ መዋቅሩ ውጤት ነው። ይሁንና ሉዓላዊ መዋቅሩ የኢኮኖሚያዊ መዋቅሩን ብቻ እንደሚያንጸባርቅና ፍዝ፤ ገለልተኛ፤ በኢኮኖሚያዊ መዋቅሩ፤ በመደቦችና በሥርዐተ ማኅበሩ መልክ ላይ ምንም ተጽዕኖ ሊያሣርፍ እንደማይችል ተደርጐ መገመት የለበትም፤- በምንም ዐይነት። ባፋራሹ፤ አንድ ጊዜ ሉዓላዊ መዋቅሩ መደበኛ መልኩን ከያዘ አዲሱ ኢኮኖሚያዊ መዋቅር መልክ እንዲይዝና እንዲጠነክር፤ በተጨማሪም አዲሱ

ሥርዐተ ማኅበር የቀድሞውን ኢኮኖሚያዊ መዋቅርና የቀድሞ መደቦችን እንዲያጠፉ የሚያደርግ እጅግ የበረታ ሀይል ይኖረዋል።

ኤኮኖሚያዊ መዋቅሩ ሉዓላዊ መዋቅሩን የሚፈጥረው ራሱን እንዲያገለግል፣ መደበኛ መልኩን ለመያዝና ለመጠንከር እንዲያግዘው፣ ነባሩንና በማጣጣር ላይ ያለውን ኢኮኖሚያዊ መዋቅር ከቆየው ሉዓላዊ መዋቅሩ ጋር ለማጥፋት አብሮት እንዲታገል ነው። ግና ሉዓላዊ መዋቅሩ ይህን ተራዳኢነቱን ከተወ፣ ለኢኮኖሚያዊ መዋቅሩ ደጀንና ተከላካይ መሆኑን አቁሞ ግዴለሽነትን ካሣየ ብሎም መደቦችን ሁሉ በእኩል ዐይን ከተመለከተ፣ ዋጋውን ያጣል። ሉዓላዊ መዋቅር መሆኑም ይቀራል።

በዚህ ረገድ ቋንቋ በአያሌ ከሉዓላዊ መዋቅሩ ይለያል። ቋንቋ በማኅበረሰቡ ውስጥ ያለው ያንዱ ወይም የሌላው፣ ያሮጌው ወይም ያዲሱ ኢኮኖሚያዊ መዋቅር ውጤት አይደለም። የማኅበረሰቡ ድምር የታሪክ ሂደትና የብዙ ዘመናት ኢኮኖሚያዊ መዋቅሮች ታሪክ ውጤት እንጂ። ባንድ መደብ የተፈጠረ ሳይሆን፣ በጠቅላላው ማኅበረሰብ፣ በማኅበረሰቡ ጠቅላላ መደቦች፣ በቡዙ መቶ ትውልዶች ጥረት ነው የተገኘው። ያንድን መደብ ፍላጐቶች ለማሟላት ሣይሆን፣ ጠቅላላውን ማኅበረሰብ፣ የማኅበረሰቡን ጠቅላላ መደቦች እንዲያገለግል ነው የተፈጠረ። በዚህም ምክንያት አንድ ቋንቋ ለማኅበረሰቡ አባሎች ሁሉ አንድ የሆነና ሁሉንም በጋርዮች የሚያገልግል የጠቅላላው ሕዝብ የወል ቋንቋ ነው። ስለሆነም በሰዎች ዘንድ የመገናኛ መሣሪያ እንደ መሆኑ፣ የቋንቋ ተግባራዊ ሚናው ለአንድ መደብ ልማት ለሌሎች መደቦች ጥፋት መስራት ሣይሆን ጠቅላላውን ማኅበረሰብ ብሎም የማኅበረሰቡን መደቦች ሁሉ እኩል ማገልገል ነው። ለዚህም ሣይሆን አይቀርም፣ አንድ ቋንቋ የጥንቱን ሟች ሥርዐተ ማኅበርና አዲሱን አዳጊውን ሥርዓት ማኅበር፣ የጥንቱን ኢኮኖሚያዊ መዋቅርና አዲሱን ኢኮኖሚያዊ መዋቅር፣ በዝባዦችንና ተበዝባዦችን እኩል የሚያገለግለው።

የሩስያ ቋንቋ የሩስያን ከበርቴና የሩስያን የከበርቴ ባህል ከጥቅምት አብዮት በፊት በሚገባ ሲያገልግል እንደ ነበረ፣ አሁንም ኅብረተሰባዊውን ሥርዐት ማኅበርና የሩስያን ማኅበረሰብ ኅብረተሰባዊውን ባህል በሚገባ እንደሚያገለግል ሁሉ የሚያውቀው ይፋ የሆነ ጉዳይ ነው።

ስለ ኩክራንኛ፣ ሊቱአንኛ፣ ኡዝቤክ፣ ካዛክ፣ ጆርጅኛ፣ አርመንኛ፣ ክስቶንኛ፣ ላትቭኛ፣ ሞልዳቭኛ፣ ታታር፣ አዘርይባይጅንኛ፣ ባሽክርኛ፣ ተርክመንኛ፣ ስለ ሌሎችም የሶቬዬት የብሔር ቋንቋዎች አንስተን ሰለ ሩስያ ቋንቋ ያልነውን መድገም እንችላለን። እኒህ የብሔር ቋንቋዎች የየብሔሮቻቸውን የቀድሞ የከበርቴ ሥርዐተ ማኅበር ሲያገለግሉ እንደ ነበር ዛሬ አዲሱን ኅብረተሰባዊ ሥርዓተ ማኅበርም ያገለግላሉ።

ቋንቋን ከዚህ በተለየ መንገድ ልናየው አንችልም። ቋንቋ ይኖራል። ቋንቋ የተፈጠረው ማኅበረሰቡን በጠቅላላው ለማገልገል፣ በሰዎች ዘንድ ግንኙነትን ለመፍጠር፣ ለማኅበረሰቡ አባሎች የጋርዮች ሁኖ የማኅበረሰቡ አንድ ቋንቋ ለመሆን፣ በማኅበረሰቡ ውስጥ ያላቸውን መደባዊ ቦታ ሣይመለከት የማኅበረሰቡ አባሎች ሁሉ በእኩል ለማገልገል ነው። አንድ ቋንቋ ለአንድ ሕዝብ በጠቅላላው የጋርዮሽ ከመሆን ሲያፈነግጥ፣ ለአንድ ማኅበረሰባዊ ክፍል ብቻ

ጥቅም ለመስጠትና በዚህም የተነሣ በሌሎች ማኅበረሰባዊ ክፍሎች ላይ ጉዳት ወደማምጣት ሲያዘነብል፤ ዋጋውን ያጣል። ያንድ ማኅበረሰብ የመገናኛ መሣሪያ መሆኑንም ያከትምና ያንድ የተወሰነ የማኅበረሰብ ክፍል የጓዳ ቋንቋ በመሆን ይቀጭጫል፤ ይጠፋልም።

በዚህ ረገድ ቋንቋ ከሉዓላዊ መዋቅሩ ሲለይ፤ እንደ ቋንቋ ሁሉ መደብን ለይተው ከማያገለግሉት፤ የከበርቴውንና ኅብረተሰባዊውን ሥርዐተ ማኅበሮች በእኩል ከሚያገለግሉት፤ ከምርት ማከናወኛ መሣሪያዎች አይለይም።

ከዚህም በላይ ሉዓላዊ መዋቅሩ ያንድ ዘመን ውጤት ነው። ይህም ዘመን አብሮት የሚሄደው ኢኮኖሚያዊ መዋቅር የሚፈጠርበትና የሚንቀሣቀሥበት ዘመን ነው። ስለሆነም ሉዓላዊ መዋቅሩ ዕድሜው አጭር ነው። ይህ የተባለው አብሮት የሚሄደው ኢኮኖሚያ መዋቅር ሲወድቅና ሲጠፋ እሱም አብሮት ይወድቃል፤ አብሮት ይጠፋል።

ባፋራሹ ግን ቋንቋ የብዙ ዘመናት ድምር ውጤት ነው። በኒህም ዘመናት ውስጥ መልኩን እያደረጀ፤ እያበለጸገ፤ እያደገና እየጠራ ይሄዳል። ስለዚህ ቋንቋ ካንድ የኢኮኖሚያዊ መዋቅር ሆነ ሉዓላዊ መዋቅር ይበልጥ ለአያሌ ዘመናት ይኖራል። ይህም በመሆኑ የአንድ ወይም የብዙ ኢኮኖሚያዊ መዋቅሮችና የነሱም ሉዓላዊ መዋቅሮች መጥፋት ያንድን ቋንቋ መጥፋት፤ ወይም ያንድን ቋንቋ መዋቅር መደምሰስና ባዲስ ቋንቋ ማለት ነባራዊና መሠረታዊ የመድበለ ቃላት ክፍልና አዲስ የሰዋሰው ስርዓት ባለው አዲስ ቋንቋ መተካትን አያስከትልም።

ፑሽኪን ከሞተ ከመቶ ዓመት በላይ ሁኖታል። በዚህም ጊዜ በሩስያ ውስጥ ጉልታዊና ከበርቴያዊ ሥርዐቶች ተደምስሰዋል። ሌላ ኅብረተሰባዊ ሥርዐትም ተገንብቷል። ይህም ማለት ሁለት ኢኮኖሚያዊ መዋቅሮችና ሉዓላዊ መዋቅሮቻቸው ጠፍተው አዲስ ኅብረተሰባዊ ኢኮኖሚያዊ መዋቅርና ሉዓላዊ መዋቅር ተቋቁሟል። ይሁን እንጂ የሩስያን ቋንቋ ብንወስድ በዚህ ረዥም ጊዜ ምንም ያህል መሠረታዊ የሆነ ለውጥ አላሣየም። ዘመናዊው የሩስያ ቋንቋም በመዋቅሩ ፑሽኪን ከጻፈበት ቋንቋ እጅግ በጥቂቱ ነው የሚለይ።

በዚህ ጊዜ በሩስያ ቋንቋ ውስጥ የተለወጠው ነገር ምንድን ነው? የሩስያ መድበለ ቃላት በአያሌ አድጓል። ብዙ ነባር ቃላት ከመድበለ ቃላቱ ወጥቷል። ብዙ ቃላት ትርጉማቸውን ለውጠዋል። የቋንቋው የሰዋሰው ስርዓት ተሻሽሏል። ሆኖም በፑሽኪን ጊዜ የነበረው የቋንቋው መዋቅርና ነባራዊውና መሠረታዊው የመድብለ ቃላቱ ክፍል እንዳለ ለዘመናዊ የሩስያ ቋንቋ መሠረት ሆኗል።

ይህም ለመረዳት የሚያዳግት ጉዳይ አይደለም። ከቶስ፤ ከየአንዳንዱ የአብዮት ወቅት በኂላ፤ ያንድ ቋንቋ መዋቅር፤ የሰዋሰው ሥርዐቱን፤ ነባራዊውንና መሠረታዊውን የመድበለ ቃላቱን ክፍል ለማጥፋትና እንደ ሉዓላዊ መዋቅሩ ሁሉ በሌላ አዲስ መተካት የሚያስፈልግበት ምን ምክንያት አለ? «ውሀ» ን «ውሀ» «አፈር» ን «አፈር» «ተራራ» ን «ተራራ» «ሜዳ» ን «ሜዳ» «ዓሣ» ን «ዓሣ» «ሰው» ን «ሰው» «መራመድ» ን «መራመድ» «መሥራት» ን «መሥራት» «ማምረት» ን «ማምረት» «መነገድ» ን «መነገድ» - ወዘተ. የማያስብልና ሌሎች ስያሜዎች አምጡ የሚል ምን ምክንያት አለ? ባንድ ቋንቋ ውስጥ ያሉ ቃላት የሚለውጡበት

እንዲሁም የቃላቱ መቀናበር ነባሩና የሰዋሰው ሥርዓት የማይከተልበትና ሌላ ፍጹም የተለየ የሰዋሰው ስርዓት የሚሻበት ምን ምክንያት አለ? በእንደዚህ ዐይነቱ የቋንቋ ውጣ ውረድ አብዮቱ ምን ያተርፋል? ምንም ጊዜ ታሪክ ለአስፈላጊነቱ ምክንያት ያላገኘለትን ነገር አያደርግም:: በመሠረቱ ነባሩ ቋንቋና መዋቅሩ የአዲሱን ሥርዐተ ማኀበር ፍላጐቶች ማሟላት ሲችሉ እንዲህ ዐይነቱ የቋንቋ አብዮት ምን አስፈላጊት ይኖረዋል? የቆየው ሉዓላዊ መዋቅር በጥቂት ዘመናት ውስጥ መጥፋትና በአዲስ መተካት ይችላል:: ለማኅበረሰቡ የምርት ኃይላት መዳበር እንዲረዳ ይህን ማድረግ አለበትም:: ግን በማኅበረሰቡ ሕይወት ውስጥ ውዥንብር ሣይፈጠርና ማኅበረሰቡ ሣይገነጣጠል በጥቂት ዘመናት ውስጥ ነባሩ ቋንቋ ሊጠፋና በቦታው አዲስ ቋንቋ ሊተካ ይቻላል? ይህንስ ዐይነቱን አድራጐት ማን ይሞክራዋል? - ዶንኩየቴ ካልሆነ በቀር::

በመጨረሻ፤ በሉዓላዊ መዋቅሩና በቋንቋ መሀል ያለውን አንድ ጥልቅ ልዩነት እንመልከት:: ሉዓላዊ መዋቅሩ ከምርት ጋርና ከሰዎች የምርት እንቅስቃሴ ጋር ቀጥተኛ ግንኙነት የለውም ከምርት ጋር ያለው ግንኙነት ቀጥተኛ ባልሆነ በኢኮኖሚያዊ መዋቅሩ በኩል ነው:: ይህም በመሆኑ ሉዓላዊ መዋቅሩ በቀጥታና በአፋጣኝ የምርት ኃይላት የዕድገት ደረጃ ላይ ያሉ ለውጦችን አያንጸባርቅም:: በምርት ላይ የመጡትን ለውጦች በኢኮኖሚያዊ መዋቅሩ ላይ በመጡለት ለውጦች ካየ በኂላ እንጂ:: ይህም የሚያሣየን የሉዓላዊ መዋቅሩ ክበበ ተግባር ጠባብና ውሱን መሆኑን ነው::

ባፋራሹ፤ ቋንቋ ከሰዎች የምርት እንቅስቃሴ ጋር ቀጥተኛ የሆነ ግንኙነት አለው:: በምርት እንቅስቃሴውም ብቻ ሣይሆን በጠቅላላው በሁሉም የሥራ መስኮች በሁሉም እንቅስቃሴዎቹ- ከምርት እስከ ኢኰኖሚያዊ መዋቅሩ- ከኢኰኖሚያዊ መዋቅሩ እስከ ሉዓላዊ መዋቅሩ ባለው ሁሉ ቋንቋና የሰው የምርት እንቅስቃሴ ቀጥተኛ ግንኙነት አላቸው:: በዚህም ምክንያት ቋንቋ በኢኮኖሚያዊ መዋቅሩ እስኪገለጡ ሣይጠብቅ በምርት ውስጥ ያሉን ለውጦች ባፋጣኝና በቀጥታ ያንጸባርቃል:: ስለሆነም የቋንቋ ክበበ ተግባር የሰዎችን መላ እንቅስቃሴዎች የሚይዝና ከሉዓላዊ መዋቅሩ ክበበ ተግባር ይበልጥ ሰፊና ይበልጥ አጠቃላይ ነው:: በሰዎች የምርት ሕይወት ውስጥ የሚረግጠው ቦታ ይህ ወሰንህ የሌለበት ነው::

ከምርት ጋር ባለው ቀጥተኛ ግንኙነት የተነሣ አንድ ቋንቋ በተለይም የመድበለ ቃላቱ ክፍል ሁልጊዜም በመለወጥ ላይ ነው የሚገኝ:: የኢንዱስትሪና የእርሻ፤ የንግድና የጉዞ፤ የቴክኖሎጂና የሣይንስ የማያቋርጥ ዕድገት አንድ ቋንቋ መድበለ ቃላቱን በአዳዲስ ቃላትና በአገላለጽ ዘዴዎች እንዲያዳብር ይጠይቃል:: ቋንቋም እኒህን ፍላጐቶች በቀጥታ በማንጸባረቅ መድበለ ቃላቱን በአዳዲስ ቃላት ያዳብራል፤ ሰዋሰዋዊ ስርዐቱንም በሚገባ ያጠናቅራል::

ስለዚህ፤-

ሀ/ አንድ ማርክሳዊ የሆነ ቋንቋን በኢኮኖሚያዊ መዋቅሩ ላይ እንዳለው ሉዓላዊ መዋቅር አድርጐ አይመለከተውም::

ለ/ ቋንቋ ሉዓላዊ መዋቅርን ማደባለቅ ትልቅ ስሕተት መፈጸም ነው::

ጥያቄ፤ አንድ ቋንቋ ጥንትም ሆነ አሁንም የመደብ ባህርይ ያለው፤ ለአንድ ማኅበረሰብ አንድና የጋርዮሽ ያልሆነ፤ ለሁሉም ሕዝብ በመደብ አልባነት ለማገልገል የማይችል ነው የሚባለው እውነት ነው?

መልስ፤ እውነት አይደለም።

መደብ አልባ በሆነ ማኅበረሰብ ውስጥ የመደብ ቋንቋ የሚባል ነገር እንደማይኖር ለመረዳት ከባድ ነገር አይደለም። በጥንታዊው የጋርዬሽ ሥርዐተ ማኅበር መደቦች አልነበሩም። ስለሆነም የመደብ ቋንቋ የሚባል ነገር ሊኖር አይችልም። በዚያን ወቅት ቋንቋው ለጠቅላላው ማኅበረሰቡ አንድና የጋራ የሆነ ነበረ። መደብ የሚለው ጽንሰ ሐሣብ ሁሉን የሰዎችን ማኅበረሰቦች - ጥንታዊ የጋርዮሽን ጨምሮ - የሚያቅፍ ነው የሚለው ክርክር ሚዛን የሚያነሣ ክርክር አይደለም።

ከጐሣ ቋንቋዎች ወደ ነገድ ቋንቋዎች- ከነገድ ቋንቋዎች ወደ ብሔረሰብ ቋንቋዎች- ከብሔረሰብ ቋንቋዎች ወደ ብሔር ቋንቋዎች ባለው ተከታታይ ዕድገት የትም በየትኛውም የዕድገት ደረጃ፤ ቋንቋ ባንድ ማኅበረሰብ ውስጥ ባለው የመገናኛ መሣሪያነት ሚናው፤ ያሉበትን የተለያዩ ማኅበረሰባዊ እርከኖች ሣይመለከት አባላቱን ሁሉ እኩል የሚያገልግል የአንድ ማኅበረሰብ የጋርዮሽ የሆነ አንድ ቋንቋ ነው።

እዚህ ላይ የጠቀስኩት፥ የባርያና የመካከለኛው ዘመን ግዛቶችን ማለት የሣይረስን ወይም የትልቁ እስክንድርን ወይም የቄሣርን ወይም የታላ ቁርሻርለስን የራሳቸው ኢኮኖሚያዊ አቋሞች ያሏቸውንና ኃላፊ፥ ቋሚ ያልሆኑ ወታደራዊ አስተዳደራዊ ግዛቶችን አይደለም። እኒህ ግዛቶች ለመላው ግዛቶች የጋርዮሽ የሆነ አባላቱ በሙሉ ሲሰሙት የሚችሉ አንድ ቋንቋ አልነበራቸውም። ሊኖራቸውም አይችልም ነበረ። እኒህ ግዛቶች የራሣቸውን ዓይነት ሕይወት የሚኖሩና ለየራሣቸው የራሳቸው ቋንቋዎች ያሏቸው የነገዶችና የብሔረሰቦች ጥርቅምቅም ግዛቶች ነበሩ። ስለሆነም ስለእኒህና ስለእኒህ ዐይነቱ ግዛቶች አይደለም የምናገረው- እሱው ባጠቃላይ ስለያዟቸው ከጥንት ጀምሮ የራሣቸው ቋንቋዎችና የራሳቸው ኤኮኖሚያዊ አቋሞች ስላሏቸው ነገዶችና ብሔረሰቦች እንጂ። እኒህ ነገዶችና ብሔረሰቦች ቋንቋዎች የመደብ ቋንቋዎች ሣይሆኑ፤ ለእያንዳንዱ ነገድ ወይም ብሔረሰብ አባላት የወል የሆኑና፤ ለእያንዳንዱ ነገድ ወይም ብሔረሰብ አባላት የወል የሆኑና የእያንዳንዱም ነገድ ወይም ብሔረሰብ አባላት በምሙሉ የሚሰሟቸው ቋንቋዎች እንደ ነበሩ ታሪክ ይነግረናል።

እርግጥ ከኒህ ቋንቋዎች ጋር፤ የቋንቋ ዘዬዎችና ከዋናው ቋንቋ በመጠኑ የሚለዩ ያካባቢ ቋንቋዎች ነበሩ፤ ይሁንና እኒህ የነገዱ ወይም የብሔረሰቡ አንድና የወል የሆነው ቋንቋ ጥገኞችና በሱም ሥር የነበሩ ናቸው።

በኋላም የከበርቴው ሥርዐተ ማኅበር ሲመጣ፤ ጉልታዊው ክፍልፍል ሲያከትምና የብሔረሰብ ገበያዎች ሲቋቋሙ የብሔረሰቦች ወደ ብሔረነት መሸጋገርና የብሔረሰብ ቋንቋዎችም ወደ ብሔር ቋንቋዎች መለወጣቸው ግድ ሆነ። ታሪክ እንደሚነግረን የብሔር ቋንቋ የመደብ

ቋንቋ ሣይሆን ለብሔሩ አባላት በሙሉ የጋራ የሆነና የዛ ብሔር አንድና የወል የሆነ ቋንቋ ነው።

ቋንቋ በማኅበረሰቡ ውስጥ በመገናኛ መሣሪያነቱ የማኅበረሰቡን መደቦች ሁሉ እኩል እንደሚያገልግል ከላይ ተገልጿል። በዚህም ረገድ ለመደቦቹ ግዴለሽነትን ያሣያል ማለት ይቻላል። ይህ ማለት ግን ሰዎች፤ ልዩ ልዩ የማኅበረሰቡ ክፍሎች፤ መደቦች ለቋንቋ ግዴለሽነትን ያሣያሉ ማለት አይደለም። ቋንቋውን የራሳቸውን ፍላጐቶች ለማሟያ ሊያውሉት ይጥራሉ። የራሳቸውን ዘዬዎች፤ የራሣቸውን ልዩ ልዩ ቃላት የራሣቸውን የአባባል ፈሊጦች ሊጭኑበት ይሞክራሉ። ራሣቸውን ከሕዝብ ያገለገሉትና ሕዝብን የሚጠሉት ሐብት ያካበቱት መደቦች ከፍተኛ አባሎች፤ መሣፍንቱ የከበርቴው መደብ ከፍተኛ አባሎች በቋንቋ ላይ በሚያደርጉት የተጠቀሰው ዐይነት ሙከራ ከሕዝብ ራሣቸውን ለይተው ለማሣየት ይሻሉ። «መደባዊ» የቋንቋ ዘዬዎች፤ የጓዳ ቋንቋዎች በከፍተኛ እርከን ላይ ያለው የማኅበረሰብ ክፍል «ቋንቋዎች» ይፈጠራሉ። እኒህም የቋንቋ ዘዬዎችና የጓዳ ቋንቋዎች በቃልም ሆነ በጽሑፍ ቋንቋ እየተባባሉ ይጠራሉ፤ - በስሕተት። «የመሣፍንቱ ቋንቋ» «የከበርቴው ቋንቋ» ባንጻሩም፤ «የወዝ አደሩ ቋንቋ» ወይም የ «አርሶ አደሩ ቋንቋ» የሚሉ አሉ - በስሕተት። ከዚህም የተሳሳተ አባባል በመነሣት አንዳንድ ጓዶች አንድ ብሔራዊ ቋንቋ መደብን ሣይመለከት የአንድ ብሔርን መደቦች በሙሉ ሊያገለግል ይችላል ሲባል እውነት አይመስላቸውም፤ ሊኖር የሚችለውም የመደብ ቋንቋ ብቻ ሊሆን እንደሚችል ይናገራሉ።

ግን ለኔ እንደሚመስለኝ ከዚህ የከፋ ስሕተት የለም። የተባሉት የቋንቋ ዘዬዎችና የጓዳ ቋንቋዎች ሊባሉ ይችላሉ? በፍጹም። ለምን ቢባል አንደኛ ነገር የተባሉት የቋንቋ ዘዬዎችና - የጓዳ ቋንቋዎች የራሣቸው የሆነ የሰዋስው ስርዓትና ነባራዊና መሠረታዊ መድበለ ቃላት የሏቸውም፤ - እኒህን ነገሮች የሚበደሩት ከብሔራዊ ቋንቋ ነው። ሁለተኛ እኒህ የቋንቋ ዘዬዎችና የመሣፍንቱ የጓዳ ቋንቋዎች በተወሰነ አካባቢ ስለሚነገሩና የሚጠቀሙባቸውም ያንድ መደብ ከፍተኛ አባላት ብቻ ስለሆኑ ለማኅበረሰቡ በመላ የጋርዮሽ የመገናኛ ቋንቋ ሊሆኑ አይችሉም። ለመሆኑም ምንድን ነው ያላቸው? የመሣፍንቱን ወይም የከበርቴውን ከፍተኛ አባሎች ልዩ ልዩ ጠባዮች የሚያጸባርቁ፤ በብሔራዊው ቋንቋ ውስጥ ሰፊው ሕዝብ ከሚጠቀምባቸው የተለዩ የቃላት ስብስቦች፤ የአገላለጽ ዘዬዎችና የሐረግ ልዩ ልዩ አሰካኮች የሏቸው። አንዳንድ የውጭ ቃላትም ይገኙባቸዋል። ነገር ግን የሚጠቀሙባቸው አብዛኞቹ ቃላትና የሰዋስው ስርዓት ሰፊው ሕዝብ በጋርዮሽ ከሚጠቀምበት ብሔራዊ ቋንቋ የተወሰደ ነው። በዚህም ምክንያት የቋንቋ ዘዬዎችና የጓዳ የጋርዮሽ ከሆነው ከብሔራዊ ቋንቋው የሚሠርጹና በራሣቸው ለመቆም ምንም የቋንቋ ነጻነት የሌላቸውና ባሉበት መበስበስ የማይቀርላቸው ናቸው። የቋንቋ ዘዬዎችና የጓዳ ቋንቋዎች ብሔራዊውን ቋንቋ አስፈንግጠው፤ እሱን ሊተኩ ወደ ሚችሉ ራሳቸውን ወደ ቻሉ ነጻ ቋንቋዎች ይለወጣሉ ማለት የታሪክን ሂደት አለማወቅና ኢማርክሲያዊ መሆን ነው።

አንዳንድ ጓዶች ሴንት ማክስ (St Max) ከተባለው ከማርክስ ጽሑፍ ከበርቴዎች «የራሳቸው ቋንቋ» አላቸው። ይህም ቋንቋ «የከበርቴው ውጤት ነው» ማለትም በንግድ፤ በመሸጥና በመለወጥ መንፈስ የተመላ ነው የሚለውን አንቀጽ ይጠቅሳሉ። ይህን

*ማድረጋቸውም ማርክስ ቋንቋ «የመደብ ጠባይ» አለው ብሎ ያምናል የሚል ሀሣባቸውን ለማሣመንና የአንድ የወል የሆነ ብሔራዊ ቋንቋን መኖር ለመካድ ነው። እኒሁ ጓዶች ነገሮችን አገላብጠው ማየት ቢችሉ ኖሮ ማርክስ በዚሁ ጽሑፍ ውስጥ አንድ ብሔራዊ ቋንቋ የሚሠርጽበትን ሁኔታዎች ሲያስረዳ «ከኢኮኖሚና ፖለቲካ ባንድ መሰብሰብና መደደር የተነሣ የአካቢ ቋንቋዎች ወደ አንድ ብሔራዊ ቋንቋነት ሊሰበሰቡ» እንደሚችሉ የተናገረበትን ሌላ አንቀጽ ሊጠቅሱ ይችሉ ነበር።*

*ማርክስ የአንድ ብሔራዊ ቋንቋን አስፈላጊነት እንደመገንዘቡ፤ የቋንቋ ዘዬዎች የከፍተኛው ብሔራዊ ቋንቋ ዝቅተኛ መኮችና ጥገኞች መሆናቸውን ያውቅ ነበር።*

*ታድያ ነገሩ እንዲህ ከሆነ ማርክስ «የከበርቴ ውጤት» የሚለው የከበርቴ ቋንቋ ምን ሊሆን ይችላል? ማርክስ የራሱ የቋንቋ መዋቅር እንዳለው እንደ ብሔራዊ ቋንቋ አድርጐ ቆጥሮታል? - ፍጹም። ማርክስ ሊል የፈለገው ከበርቴው ብሔራዊውን ቋንቋ በመሸጥ በመለወጥ የቋንቋ ዘይቤ በክሎታል ነው። ማርክስ ሊል የፈለገው ከበርቴው የመሸጥ የመለወጥ የንዳ ቋንቋ አለው ነው።*

*እና እኒህ ጓዶች ማርክስ ያለውን እንዳልተረዱ እንገነባለን። የስሕተታቸውም ምክንያቱ ማርክስ ያለውን የጠቀሱት አንድ ማርክሳዊ ማድረግ እንደሚገባው ወደ ጉዳዩ ፍሬ ነገር ጠልቀው ሳይሆን እንደ አንድ ቀኖናዊ በመሆኑ ነው።*

*«በእንግሊዝ ሀገር የወዝ አደሩ ሁኔታ» ከሚለው የኤንግልስ ጽሑፍም በእንግሊዝ ሀገር «የሠራተኛው መደብ ቀስ በቀስ ከእንግሊዝ ከበርቴ የተለየ ዘር ሁኗል» «ሠራተኛው ከከበርቴው በተለየ የቋንቋ ዘዬ ነው የሚነገረው፤..... የተለዩ ሀሣቦችና ምኞቶች፤ የተለዩ ባህሎችና የሞራል ሕግጋት፤ የተለየ ሃይማኖትና የተለየ ፖለቲካ አለው።» የሚለውን የሚጠቅሱም አሉ። ከዚህም በመነሣት አንዳንድ ጓዶች ኤንግልስ የወል የሆነ ብሔራዊ ቋንቋ አስፈላጊነትን መካዱን፤ ቋንቋ የ «መደብ ጠባይ» አለው ብሎ ማመኑን ይገልጻሉ። ይሁንና በተጠቀሰው ጽሑፍ ኤንግልስ የተናገረው ስለ ቋንቋ ዘዬዎች እንጂ ስለ ቋንቋዎች አልነበረም። ይህም ሲሆን የቋንቋ ዘዬዎች የብሔራዊ ቋንቋው ተቀጥላ መሆናቸውንና ብሔራዊውን ቋንቋ ሊተኩ አለ መቻላቸውን በሚገባ እያወቀ ነው። ጽሑፉን የጠቀሱ ጓዶች በቋንቋና በቋንቋ ዘዬዎች መሀል ያለውን ልዩነት በወጉ የተረዱ አይደሉም።*

*የተባሉት ጓዶች የጠቀሱትን የኤንግልስን ጽሑፍ በሚገባ አላጤኑትም። ኤንግልስ በጽሑፉ የተናገረው ስለ «መደብ ቋንቋዎች» ሣይሆን፤ ባብዛኛው ስለ መደብ አስተሳሰቦች፤ ምኞቶች፤ ባህሎች፤ የሞራል መርሆዎች፤ ሃይማኖት፤ ፖለቲካ - ነበረ። የከበርቴውና የወዝ አደሩ አስተሳሰቦች፤ ምኞቶች፤ ባህሎች፤ የሞራል መርሆዎች ሃይማኖቶችና ፖለቲካዎች በቀጥታ የሚጻረሩ ነገሮች መሆናቸው እርግጥ ነው። ግን ይህ ከብሔራዊ ቋንቋ ወይም ከቋንቋ የ «መደብ ጠባይ» ጋር ምን ግንኙነት አለው? በማኅበረሰቡ ውስጥ የመደብ ቅራኔዎች መኖር ቋንቋ የ «መደብ ጠባይ» እንዳለው የሚያስተማምኑ፤ ወይም የአንድ ብሔራዊ ቋንቋን አስፈላጊነት የሚቃወሙ ሀሣቦችን ሊያመጣ ይችላል? ማርክሲዝም ምንም በአንድ ብሔር*

ውስጥ የመደብ ቅራኔዎች እንደሚኖሩ ቢገነዘብም፣ ሁሉንም መደቦች በወል የሚያገለግል አንድ ቋንቋ የብሔሩ ዋና ዋና መለዮዎች ከሆኑት ነገሮች አንዱ እንደሆነ ያውቃል።

የላፋርግ ን «የፈረንሣይኛ ቋንቋ ከአብዮቱ በፊትና በኋላ» የሚለውን ጽሑፉን የሚጠቅሱና ላፋርግ ቋንቋ «የመደብ ጠባይ» አለው ብሎ እንደሚያምንና ላንድ ሕዝብ የጋራ የሆነ አንድ ብሔራዊ ቋንቋ ማስፈልጉን እንደሚክድ አድርገው የሚናገሩም ጓዶች አሉ። ግን ይህ ትክክል አይደለም። እርግጥ ላፋርግ ስለ «ታላላቅ ሰዎች ቋንቋ» ስለ «መሣፍንት ቋንቋ» ይናገራሉ። ይሁንና እኒህ ጓዶች የረሱት፣ ላፋርግ፣ በቋንቋና በጓዳ ቋንቋ መሀል ስላለው ልዩነት ብዙም ያልተጨነቀውና የቋንቋ ዘዬዎችን አንዳንድ ጊዜ «አርቲፊሻል ቋንቋዎች» አንዳንድ ጊዜ የ «ጓዳ ቋንቋዎች» የሚለው ላፋርግ፣ በዚህ ጽሑፉ ውስጥ በማያሻማ ሁኔታ «የመሣፍንቱ መለዮ የሆነው አርቲፊሻል ቋንቋ የሠረጸው ለሁሉም ሕዝብ የጋርዮሽ ከሆነው፣ ከበርቴውና ሠራተኛው፣ ከተሜውና ገጠሬው ከሚናገሩበት ቋንቋ ነው።» ያለውን ነው።

ላፋርግ ለጠቅላላው ሕዝብ የወል የሆነ ቋንቋ መኖሩንና አስፈላጊነቱንም ተገንዝቧል። በተጨማሪም «የመሣፍንቱ ቋንቋ» ና ሌሎችም የቋንቋ ዘዬዎችና የጓዳ ቋንቋዎች አንድን ሕዝብ ዳር እስከ ዳር ለሚያገለግለው አንድ የወል ቋንቋ ጥገኞች መሆናቸውንም በሚገባ ያውቃል።

በመሆኑም ላፋርግን የጠቀሱ ጓዶች ዓላማቸውን እንደሣቱ ያስተውሏል። ጥንት በእንግሊዝ ሀገር ባላባቶች ለ «ዘመናት» በፈረንሣይኛ ያናገሩ በነበረበት ጊዜ ሰፊው የእንግሊዝ ሕዝብ በእንግሊዝኛ ነበር የሚናገር። ይህም ቋንቋ «የመደብ ጠባይ» እንዳለው የሚያሣይና ለአንድ ሕዝብ በሙሉ የወል የሆነን ቋንቋ አስፈላጊነት የሚሽር ጉዳይ ነው እየተባለ ለክርክር ይጠቀሣል። ይሁንና ይህ አንድ ውሱን ድርጊት የሚያከራክር ጭብጥም አይደለም። በመጀመሪያ ነገር፣ በዚያን ጊዜም ቢሆን ሁሉም ባላባቶች ፈረንሣይኛን አይናገሩም ነበር። ከሸንጐ አደባባዮችና ከአስተዳደር ዋና ከተሞች ጋር ግንኙነት የነበራቸው የጉልተኛው መደብ ከፍተኛ አባላት ብቻ እንጂ። ሁለተኛ እኒህም እንኳን ቢሆኑ ይናገሩት የነበረው አንድ የተለየ «የመደብ ቋንቋን» ሣይሆን የፈረንሣይ ሕዝብ በሙሉ የሚጠቅምበትን ተራ ቋንቋ ነበረ። ሶስተኛም ከጊዜ በኋላ ይህ የፈረንሣይኛ ቋንቋ ወረት ደብዛው ጠፍቶ ለእንግሊዝ ሕዝብ በሙሉ የወል በሆነው በእንግሊዝኛ ቋንቋ መተካቱን እናውቃለን። ለመሆኑ በዚህ ጉዳይ ላይ የሚከራከሩት ጓዶች የሚሉት የእንግሊዝ ባላባቶች ከእግሊዝ ሕዝብ ጋር «ለዘመናት» ሐሳብ ይለዋወጡ የነበሩት በአስተርጓሚዎች አማካይነት ነበር፣ ነው? የእንግሊዝ ሕዝብ የወል የሆነ ቋንቋ አልነበረውም ነው? የፈረንሣይ ቋንቋ በእንሊዝ ሀገር ከፍተኛው እርከን ላይ የነበረው የማኅበረሰብ ክፍል ቋንቋና የጉልተኛውን መደብ ከፍተኛ አባላት ጠባብ ክበብ ከማገልገል ያለፈ አገልግሎት አልነበረውም ነው? እንዲህ ባለውሱን ድርጊት ላይ ሀሣብን መሥርቶ ላንድ ሕዝብ በጠቅላላው የወል የሆነ አንድ ቋንቋ መኖሩንና ማስፈለጉን እንደምን መካድ ይቻላል?

በዛሩ ሸንጐና በማኅበረሰቡ ከፍተኛ አባላት ዙርያ ያሉ የሩስያ መሳፍንት በፈረንሣይኛ ቋንቋ የሚናገሩበት ጊዜ ነበር። የሩስያ ቋንቋ በሚናገሩበት ጊዜ ወደ ፈረንሣይ የሚያስባቸው ሩስያኛውንም በፈረንሣይኛ የድምጽ ቃል የሚያስኬዱት፣ በዚሁም የሚኩራሩ ነበሩ። ግን ይህ

ማለት በዚያን ጊዜ ለሩስያ ሕዝብ ሁሉ የጋራ የሆነ ቋንቋ እንጂ «የመደብ ቋንቋ» አይደለም የሚኖረው ስንል ተረት ማውራታችን ሣይሆን ገሀድ እውነታን ማጽደቃችን ነው።

ጓዶቻችን ግን በትንሹ ሁለት ስሕተቶችን ፈጽመዋል። በመጀመርያ ቋንቋና ሉዓላዊ መዋቅርን አደባልቀዋል። ሉዓላዊ መዋቅሩ የመደብ ጠባይ ስላለው፤ ቋንቋንም የመደብ ቋንቋ መሆን ካለበት፤ ሕዝቡንም በወል ሊያገለግል አይችልም ነው የሚሉ። ግን ቀደም ብዬ እንደተናገርኩት ቋንቋና ሉዓላዊ መዋቅር የተለያዩ ፅንሰ ሐሣቦች ናቸው፤ አንድ ማርክሣዊም እኒህን ማደባለቅ የለበትም።

ሁለተኛው ስሕተታቸው የከበርቴውንና የወዝ አደሩን ፍላጐቶች ቅራኔ በመሀላቸው የሚካሄደውን ጠንካራ የመደብ ትግል እንደ ማኅበረሰቡ መፈራረስ ማየታቸውና የተጻራሪዎቹ መደቦች መሀል ያለውን ግንኙነት ፍጹም የተቋጠረ አድርገው መቁጠራቸው ነው። ማኅበረሰቡ በመደቦች ስለ ተከፋፈለና አንድ ወጥ የሆነ ማኅበረሰብ ስለሌለ አንድ ለማኅበረሰቡ የወል የሆነ ቋንቋ ማለት ብሔራዊ ቋንቋ አያስፈልግም ይላሉ።

እነሱ እንደሚሉት ማኅበረሰቡ ከፈራረሰ የጋራ የሆነ ብሔራዊ ቋንቋ ከሌለ መደቦችና «የመደብ ቋንቋዎች» ብቻ ሊኖሩ ነው። ብሎም እያንዳንዱ «የመደብ ቋንቋ» የራሱ «የመደብ ሰዋሰው» - ማለትም «የወዝ አደር ሰዋሰው» ወይም «የከበርቴ ሰዋሰው» የሚባል ነገር ሊኖረው ነው። እውነቱ ግን እንዲህ ያለ ሰዋሰው የትም አለመገኘቱ ነው። ይሁንና ይህ እኒህን ጓዶች አያሳስባቸውም። በነሱ እምነት እንዲህ ዓይነቱ ሰዋሰው አንድ ቀን ሊፈጠር ይችላል ብለው ያስባሉ።

አንድ ጊዜ በሀገራችን፤ ከጥቅምት አብዮት በኋላም የነበሩ ባቡር መንገዶች ቀድሞ የከበርቴ ባቡር መንገዶች ነበሩና፤ ለኛ ለማርክሣውያን አገልግሎት ሊውሉ አይችሉም፤ ወድያ ተሰባብረው ተጥለው አዳዲስ «ወዝ አደራዊ» ባቡር መንገዶች መሠራት አለባቸው ያሉ «ማርክሣውያን» ነበሩን!

በማኅበረሰብ፤ በመደቦች፤ በቋንቋ ጉዳዮች ላይ የሚሠነዘሩ እንዲህ ዐይነቶቹ ጥሬ ሥርዐተ አልባዊ አስተያየቶች ከማርክሲዝም ጋር ምንም ግንኙነት የላቸውም። ይሁን እንጂ በአንዳንድ ጓዶች ውዥንብራም አእምሮ ውስጥ እንዲህ ያሉ አስተያየቶች እስከዛሬም ይጉላላሉ።

ጠንካራ የመደብ ትግል በመኖሩ ምክንያት አንዳቸው ካንዳቸው በኢኮኖሚ ባልተያያዙ መደቦች ማኅበረሰቡ ተከፍሏል ማለት ትልቅ ስሕተት ነው። የከበርቴ ሥርዐተ ማኅበር እስካለ ከበርቴውና ወዝ አደሩ በኢኮኖሚ ገመዶች የተሣሠሩት የከበቴ ማኅበረሰብ ክፍሎች ናቸው። ከበርቴው እንደ ልቡ የሚያሠራው የጉልበት ሠራተኛ ከሌለው ሊኖርና ሊበለጽግ አይችልም። ወዝ አደሩም ራሱን ለከበርቴው ካልሸጠ ለመኖር አይችልም። የኢኮኖሚ ግንኙነታቸው መቋረጥ የምርት መቋረጥ ማለት ይሆናል፤ የምርት መቋረጥም የማኅበረሰቡ መጥፋት፤ የራሣቸው የመደቦች መጥፋት ማለት ይሆናል። በመሠረቱ ማንም መደብ ቢሆን ራሱን በራሱ ሊያጠፋ አይፈልግም። ስለ ሆነም የመደብ ትግሉ ምንም የከረረ ቢሆን የማኅበረሰቡን መጥፋት አያስከትልም። ጓዶችን ስለ ማኅበረሰብ መፈራረስ ስለ «መደብ» ቋንቋዎችና ና ስለ «መደብ

ሰዋሰዎች» ያሏቸውን ተረታ ተረት ሃሳቦች የመነጨው ማርክሲዝምን አለማወቃቸና ስለ ቋንቋ ተፈጥሮ ምንም ለመረዳት አለመቻላቸው ሊሆን ይችላል።

ሌኒን በከበርቴ ሥርዐተ ማኅበር ሁለት ባህሎች - የከበርቴ ና የወዝ አደር መኖራቸውን እንደተናገረና የብሔራዊ ባህል መፈክርም የብሔረተኞች መፈክር ነው እንዳለ የሚጠቅሱ አሉ። ይህ ልክ ነው። ሌኒንም አልተሣሣተም። ግን ይህ ከቋንቋ «የመደብ ጠባይ» ጋር ምን ግንኙነት አለው? እኒህ ጓዶች ሌኒን በከበርቴ ሥርዐተ ማኅበር ውስጥ ስላሉ ሁለት ባህሎች ማውሣቱን መጥቀሣቸው፤ ማኅበረሰቡ ውስጥ የከበርቴና የወዝ አደር የሚባሉ ሁለት ባህሎች መኖር፤ ቋንቋና ባህሎች የተያያዙ ነገሮች በመሆናቸው፤ ወደ ሁለት ቋንቋዎች ባህሎች የተያያዙ ነገሮች በመሆናቸው፤ ወደ ሁለት ቋንቋዎች ማምራቱን ለመግለጽና ከዚህም አያይዞ ሌኒን የአንድ ቋንቋ አስፈላጊነትን መካዱን ብሎም በ «መደብ ቋንቋዎች» ማመኑን ለማስረዳት ነው። እኒህ ጓዶች እዚህ ላይ የሠሩት ስሐት ቋንቋና ባህልን ማደባለቃቸው ነው። ቋንቋና ባህል ሁለት የተለያዩ ነገሮች ናቸው። ባህል ከበርቴያዊ ወይም ኅብረተሰባዊ ሊሆን ይችላል። ቋንቋ ግን በመገናኛ መሣሪያነቱ ምን ጊዜም ለአንድ ሕዝብ በጠቅላላው የወል የሆነ ከበርቴያዊውንና ኅብረተሰባዊውን ባህል ሊያገለግል የሚችል ነው። የሩስያ፤ የዩክሬንያ፤ የኡዝቤክ ቋንቋዎች ከጥቅምት አብዮት በፊት የኒህን ብሔሮች የከበርቴውን ባህሎች ሲያገለግሉ እንደ ቆዩና ዛሬ ደግሞ ኅብረተሰባዊውን ባህል ማገልገላቸው ይፋ እውነት አይደለም? የሁለት የተለያዩ ባህሎች መኖር ወደ ሁለት የተለያዩ ቋንቋዎች የሚያመራና የአንድ ቋንቋን አስፈላጊነት የሚያፈርስ ነው እሚሉቱ እኒህ ጓዶች ባያሌው ተሳስተዋል።

ሌኒን ስለ ሁለት ባህሎች በተናገረው ጊዜ የተነሣው የሁሉት ባህሎች መኖር የአንድ ቋንቋን መኖር አስፈላጊነት ወደ መካድና ወደ ሁለት ቋንቋዎች ምስረታ ሊያመራ ስለማይችል አንድ ቋንቋ መኖር አለበት ከሚለው ጭብጥ ላይ ነበር። ቡንዲስቶች ሌንኒን የአንድ ብሔራዊ ቋንቋን አስፈልጊነት ትክዳለህ፤ - ባህልንም ኢብሔራዊ አድርገህ ነው የምትመለከት ባሉት ጊዜ፤ ሌኒን ባያሌው መቃወሙንና እሱ የሚታገለው የከበርቴዎችን ባህል እንጂ ብሔራዊ ቋንቋዎችን (- አስፈላጊነታቸውን የማያከራክር መሆኑን ስለሚያምን-) እንዳልሆነ መግለጹን እናውቃለን። አንዳንድ ጓዶች በቡንዲስቶች እግር ተተክተው እድኒህ ያለ ሀሣብ ሲያናፍሱ መስማታቸው የሚገርም ነገር ነው።

ሌኒን አስፈላጊነቱን ክዷል ስለ ተባለው አንድ የብሔር ቋንቋ፤ ከዚህ ቀጥሎ የተናገረውን ማስተዋሉ ይበጃል።

«ቋንቋ እጅግ አስፈላጊ የሆነው የሰው የመገናኛ መሣሪያ ነው። የቋንቋ አንድነትና ያልታገደ እድገቱ ለዘመናዊው የወረት ክምችት ምቹ ለሆነው ለእውነተኛ ነጻ ሰፊ የንግድ ልውውጥና ለነጻና ለሰፊ የሕዝቦች በየ ልዩ ልዩ መደቦች መከፋፈል እጅግ ከሚያስፈልጉት ጉዳዮች አንዱ ነው።»

ከዚህ ማስተዋል እንደሚቻለው ጓዶች የሌኒን አስተያየቶች በአያሌው አሳብረዋል።

በመጨረሻም እስታሊን ባንድ ጽሑፍ «ከበርቴው መደብና ብሔራዊ ፓርቲዎቹ በዚህ ጊዜ የኒህ ብሔሮች አንቀሣቃሽና መሪ ኃይላት ይሆናሉ።» ያለውን የሚጠቅሱ አሉ። ይህም ልክ ነው። የከበርቴው መደብና ብሔራዊና ፓርቲው በእርግጥ የከበርቴውን ባህል ይመሩታል፤ - ልክ የወዝ አደሩ መደብና ዐለም ዐቀፋዊው ፓርቲው የወዝ አደሩን ባህል እንደሚመሩት ማለት ነው። ግን ይህ ከቋንቋ «የመደብ ጠባይ» ጋር ምን ግንኙነት አለው? እኒህ ጓዶች ብሔራዊ ቋንቋ የብሔራዊ ባህል አንድ ዐይነት መልክ መሆኑንና ብሔራዊ ቋንቋ በከበርቴያውያን ኅብረተሰባዊውን ባህል ባንድ እንደሚያገለግል አያውቁም? ደሞስ እኒሁ ጓዶች የታወቀውን የማርክሣውያንን ቅርጸ ሀሣብ፤ ማለትም የዛሬው የሩስያ፤ የዩክራንያ፤ የቤሉሩስያና የሌሎችም ባህሎች በይዘታቸው ኅብረተሰባዊ በቅርጻቸው ማለት በቋንቋቸው ብሔራዊ መሆናቸውን አልተረዱም።?

እዚህ ላይ ጓዶች የፈጸሙት ስሕተት በባህልና በቋንቋ መሀል ያለውን ልዩነት አለማየታቸውና፤ ቋንቋ በተለያዩ ዘመናት አዲሱንና የጥንቱን ባህል እኩል በማገልገል ነባር መልኩን ይዞ በሚቆይበት ጊዜ፤ ባህል በየአንዳንዱ አዲስ የማኅበረሰብ እድገት ዘመን ይዘቱን እንደሚለውጥ አለመረዳታቸው ነው።

ስለዚህም፤-

*ሀ/ ቋንቋ በመገናኛ መሣሪያነቱ ለሁሉም አባላት የጋርዮሽ የሆነ ምንጊዜም ያንድ ማኅበረሰብ አንድ ቋንቋ ሁኖ ይቆያል።*

*ለ/ የዋናው ቋንቋ ተቀጥላዎችና ጥገኞች የሆኑት የቋንቋ ዘዬዎችና የጓዳ ቋንቋዎች መኖር የአንድ ብሔር ሕዝብ የጋርዮሽ የሆነ ያንድ ብሔራዊ ቋንቋን መኖር የሚያስኬድ ሣይሆን የሚያረጋግጥ ነገር ይሆናል።*

*ሐ/ ቋንቋ «የመደብ ጠባይ» አለው ማለት ስሕተትና ኢማርክሣዊ አስተሣሠብ ነው።*

*ጥያቄ፤ የቋንጣ ጠባያዊ መልኮች ምንድር ናቸው?*

*መልስ፤ ቋንቋ በማኅበረሰብ ዘመነ ኅላዌ ሁሉ ያለ አንድ የማኅበረሰብ ክስተት ነው። ከማኅበረሰብ መመሥረት ጋር ይመሠረታል። ከእድገቱ ጋር ያድጋል። ከሞቱም ጋር ይሞታል። ቋንቋ ከማኅበረሰብ ተነጥሎ አይገኝም። ይህም በመሆኑ ቋንቋና የእድገቱ ሕግጋት በደንብ ሊጠና የሚችለው ከማኅበረሰቡ ታሪክና የቋንቋው ባለቤት ፈጣሪና አንዋሪ፤ ከሆነው ሕዝብ ታሪክ ጋር ባንድ የተጠና እንደሆነ ነው።*

*ቋንቋ በሰዎች ዘንድ የእርስ በርስ ሀሣብ መለዋወጫ የመግባቢያ መሣሪያ ነው። ከማሰብ ጋር ባለው ቀጥተኛ ግንኙነት፤ ቋንቋ፤ በቃላትና በዐረፍተ ነገር ውስጥ በተቀናበሩ ቃላት ይቀመራል። ይህም የማሰብና የሰው የግንዛቤ እንቅስቃሴ ክንውን ውጤት ነው። በመሆኑም በሰዎች ማኅበረሰብ ውስጥ የሃሣብ መለዋወጥ ለማድረግ ያስችላል።*

*የሀሳብ መለዋወጥ ምንጊዜም የማያቋርጥ እጅግ አስፈላጊ ነገር ነው፡፡ ያለ ሀሳብ መለዋወጥ ሰዎች ከተፈጥሮ ኃይላት ጋር የሚያደርጓቸውን ትግሎችና አስፈላጊዎችን ቁሣዊ ዕሴቶች ለማምረት፡፡ ያለ ሀሣብ መለዋወጥ የማኀበረሰቡን የምርት እንቅስቃሴ መቃናት ማረጋገጥ አይቻልም፡፡ ያለ ሀሣብ መለዋወጥ የምርት ማምረት ሕልውናም ያከትማል፡፡ በዚህም ምክንያት ሀሣብ መለዋወጥ የሚቻለው በቋንቋ ነውና ያንድ ማኀበረሰብ ማምረቱን የግድ ያቆማል፣ ራሱም ይፈራርሣል፣ ግባ ተመሬቱም ይፈጸማል፡፡ በዚህ ረገድ፣ ቋንቋ የመገናኛ መሣሪያ ከመሆኑ ጋር የትግልና የማኀበረሰብ እድገት መሣሪያ ነው፡፡*

*ባንድ ቋንቋ ውስጥ ያሉ ቃላት ባንድ ላይ ተጠቃለው የቋንቋውን መድበለ ቃላት ይሆናሉ፡፡ በመድበለ ቃላቱ ውስጥ ዋናውን ክፍል የያዘው፣ ሥርወ ቃላቱን ዐቢይ ነገር አድርጐ የያዘው መሠረታዊ የቃላት ስብስቡ ነው፡፡ ይህ ከመድበለ ቃላቱ አነስተኛው ክፍል ነው፡፡ ሁኖም ለረዥም ጊዜ የሚቆየውና ቋንቋው በየጊዜው ለሚያክላቸው አዳዲስ ቃላት መሠረት የሚሆነው ይኸው ክፍል ነው፡፡ መድበለ ቃላቱ የቋንቋውን ሁኔታ ያንጸባረቃል፡፡ መድበለ ቃላቱ የበለጸገና የሰፋ ከሆነ ቋንቋውም የበለጸገና የሰፋ ይሆናል፡፡*

*ይሁን እንጂ መድበለ ቃላቱ በራሱ ብቻ ቋንቋውን አይሆንም፡፡ መድበለ ቃላቱ ቋንቋው የተገነባበት ጡብ ነው፡፡ ምንም እንኳን አድን ግንብ ያለ ጡብ ሊሠራም ባይችል፣ ጡብ በራሱ ብቻ ግንቡን ሊሆን አይችልም፡፡ እንዲሁም ምንም እንኳ ያለ መድበለ ቃላቱ የቋንቋ መኖር የማይታሰብ ነገር ቢሆንም፣ መድበለ ቃላቱ በራሱ ብቻ ቋንቋውን ሊሆን አይችልም፡፡ ያንድ ቋንቋ መድበለ ቃላት ትልቅ ጥቅም የሚኖረው በሰዋሰው ሥርዐት ሥር ሲውል ነው፡፡ ሰዋሰው የቃላትን ልዩ ልዩ መልክ መያዝ፣ የቃላትን በዐረፍተ ነገር መቀናበርና አንድ ቋንቋ አንድ ወጥ የሆነና ትርጉም ያለው ሙያ እንዲኖረው የሚያደርጉትን ሕግጋት ይገልጻል፡፡ ሰዋሰው፣ የቃላትን ልዩ ልዩ መልክ መያዝና ቃላት በዐረፍተ ነገር የሚቀናበሩበትን ሁኔታ የሚገልጹ ሕግጋት ስብስብ ነው፡፡ በሰዋሰው አማካይነት የሰውን ሀሣብ በቋንቋ ሸፋን ጠቅሎ በተጨባጭ መንገድ ለማቅረብ ተቻለ፡፡*

*የሰዋሰው ሕግጋት በአንድ ቋንቋ ውስጥ ለሚገኙ የተወሰኑ ቃላት ወይም ዐረፍተ ነገሮች ሣይሆን ለጠቅላላው ቃላትና ዐረፍተ ነገሮች የሚውሉ ናቸው፡፡ ሰዋሰው ቃላትንና ዐረፍተ ነገሮችን በነጠላ ከመመልከት ተገልሎ ለድምሩ ቃላትና ዐረፍተ ነገሮች - ማለት ለቃላቱ በልዩ ልዩ መልክ መገኘትና በዐረፍተ ነገሮች መቀናበር - ምክንያት ሊሰጡ የሚችሉን የወልና መሠረታዊ የሆኑ ጉዳዮችን ይይዛል፡፡ ሰዋሰው፣ የሰው አእምሮ በረዥም ጊዜ ውስጥ ከብዙ የቋንቋ ነገሮች ጨምቆ ያወጣው ነገር ነው፡፡ የሀሣብን ከፍተኛ ተግባርም ያሣያል፡፡*

*በዚህ ረገድ ሰዋሰው ሕግጋትን ሲያወጣ ነገሮችን ግዙፍ እንደሌላቸው አድርጐ በመመልከት ከግዙፍ ነገሮች ራሱን የሚያላቅቀውንና በነገሮችም መሀል ያለውን ተዛምዶ በግዙፍ ነገሮች መሀል ያለ ግዙፍ ያነሣ ግንኙነት ሣይሆን ባጠቃላይ ግዙፍ እንደሌላቸው ነገሮች ግንኙነት አድርጐ የሚወስደውን ጂኦሜትሪን ይመስላል፡፡*

*ከምርት ጋር ቀጥታ ግንኙነት እንደሌለውና ግንኙነቱ በኢኮኖሚው በኩል እንደሆነው እንደሉዓላዊ መዋቅሩ ሣይሆን፣ ቋንቋ ከሰው የምርትና የማንኛቸውም እንቅስቃሴዎቹ የሥራ*

መስኮቹ ጋር ሁሉ ቀጥታ ግንኙነት አለው። በዚህም ምክንያት ባንድ ቋንቋ ውስጥ ያሉ ቃላት በማያቋርጥ ለውጥ ላይ ይገኛሉ። ቋንቋ ለውጥ ያሉ ቃላት በማያቋርጥ ለውጥ ላይ ይገኛሉ። ቋንቋ ለውጥ ለማሳየት እንደ ሉዓላዊ መዋቅሩ ኢኮኖሚያዊ መዋቅሩ እስኪለወጥ አይጠብቅም። ኢኮኖሚያዊ መዋቅሩ በምንም ዐይነት ሁኔታ ቢገኝ ቋንቋ ለውጥ ያሣያል - በተለይም በመድበለ ቃላቱ በኩል።

ያንድ ቋንቋ መድበለ ቃላት መለወጥ እንደ ሉዓላዊ መዋቅሩ መለወጥ የቆየውን አፍርሶ አዲስ በመገንባት አይደለም። በሥርዐተ ማኅበሩ መለወጥ፤ በምርት ማደግ፤ በባህልና በሣይንስ መደርጀት መነሾ በተፈጠሩ አዳዲስ ቃላት መድበለ ቃላቱን በማዳበር እንጂ። በተጨማሪም አንዳንድ ነባር ቃላት ከመድበለ ቃላቱ እየረገፉ ሲቀሩም ከኒህ በቁጥር የበለጡ ደግሞ ይጨመራሉ። ነባርና መሠረታዊ የሆነው የመድበለ ቃላቱ ክፍል ግን በጥንት መልኩ ይቆያል። ለቋንቋው መድበለ ቃላትም መሠረት በመሆን ያገለግላል።

ለአያሌ የታሪክ ዘመናት በደንብ ሊያገለግል ሲችል፤ ነባራዊውንና መሠረታዊውን የመድበለ ቃላት ክፍል ማጥፋት የሚያስፈልግ ነገር አይደለም። ከዚህም በላይ በአጭር ጊዜ አንድ መድበለ ቃላት መፍጠር አይቻልም። በአያሌ ዘመናት ውስጥ የተጠራቀመውን ነባራዊውንና መሠረታዊውን የመድበለ ቃላት ክፍል ማጥፋት ቋንቋው እንዲበድንና በሰዎች መካከል ያለው ግንኙነትም ፍጹም እንዲቋረጥ ማድረግ ይሆናል።

በአንድ ቋንቋ ውስጥ ከነባሩና መሠረታዊው የመድበለ ቃላቱ ክፍል ይበልጥ ዳተኛ የሆነ ለውጥ የሚያሣየው የሰዋሰው ሥርዐቱ ነው። በዘመናት ውስጥ ደርጅቶ ከቋንቋው ጋር ሥግው የሆነው የሰዋሰው ሥርዐት ከነባራዊውና መሠረታዊው የመድበለ ቃላቱ ክፍል ይበልጥ ዘገምተኛ ለውጥ ያደርጋል። እርግጥ በዘመን ብዛት የሰዋሰው ሥርዐትም እየተለወጠ፤ ምላት እያገኘ ሕግጋቱን እያሻሻለ ቀጥተኛ እየሆነ አዳዲስ ሕግጋት እየቀመረ ይሄዳል። ይሁንና የሰዋሰው ሥርዐቱ መሠረታውያን ነገሮች ማኅበረሰቡን ለብዙ ዘመናት በሚገባ ማገልገል ይችላሉና ለረዥም ጊዜ እንዳሉ ይቆያሉ።

እናም የሰዋሰው ሥርዐትና ነባሩና መሠረታዊው የመድበለ ቃላቱ ክፍል የአንድ ቋንቋ መሠረት፤ የተለየ ጠባዩም ዐበይት መልኮች ይሆናሉ።

ከታሪክ እንደምንረዳው ቋንቋዎች በነባር መልካቸው የመቆየት ችሎታና፤ በጫና ከሌሎች ቋንቋዎች ጋርም እንዲዋሀዱ የሚደረግባቸውን ሙከራ ለመከላከል ከፍተኛ ኃይል አላቸው። አንዳንድ የታሪክ ዐዋቂዎች ይህን ክስተት እንደማብራራት መገረማቸውን ብቻ መግለጽ ያልፉታል። ነገሩ ግን የሚያስገርም አልነበረም። ለቋንቋዎች ጽናትና በነባር መልካቸው ለመቆየታቸው ምክንያቱ የሰዋሰው ስርዓቶቻቸውና ነባሮቹና መሠረታውያኑ የመድበለ ቃላቱ ክፍሎቻቸው ነበሩ። የቱርክ አዋሀጆች ለብዙ መቶ ዓመታት የባልካንን ሕዝብ ቋንቋዎች ለማፍረስ፤ ለመደቆስና ለማጥፋት ሞክረው ነበር። በኒህ ጊዜያትም ውስጥ በባልካን ቋንቋዎች መድበለ ቃላት ላይ ለውጥ ታይቶባቸዋል። ጥቂት የቱርክ ቃላት ላይ ለውጥ ታይቶባቸዋል። ጥቂት የቱርክ ቃላትና ያገላለጽ ዘዬዎች ታክለውባቸዋል። የወሰዷቸውም የሰጧቸውም ነገሮች አሉ። ይሁን እንጂ የባልካን ቋንቋዎች ሣይጠፉ ራሣቸውን እንደቻሉ ሊቆዩ በቅተዋል። ለምን

ቢባል የሰዋሰው ስርዓቶቻቸውና ነባሮቹና መሠረታውያኑ የመድበለ ቃላቱ ክፍሎች የኖረ መልካቸውን ለማራዘም ጽናት ስላላቸውና ለመቆየትም በመቻላቸው ነው።

ከዚህ ሁሉ እንደምንረዳው አንድ ቋንቋ ማለትም የቋንቋው መዋቅር የአንድ ዘመን ውጤት አይደለም። የአንድ ቋንቋ መዋቅር፣ የሰዋሰው ሥርዐቱና መሠረታዊ የቃላት ስብስቡ የአያሌ ዘመናት ውጤት ነው።

የዘመኑ ቋንቋ አንዳንድ መሠረታውያን ነገሮች ከባርያ ዘመን በፊት እጅግ ባረጀው ዘመን በነበረ ቋንቋ ውስጥ ይገኙ እንደ ነበር መገመት እንችላለን። የያን ጊዜው ቋንቋ ቀላል ቋንቋ ነበረ። የተወሰኑ ቃላትና ጥንታዊም ቢሆን እንኳን የራሱ የሆነ ሰዋስዋዊ ሥርዐት ነበረው።

የምርት ዕድገት መኖር፣ የመደቦች ብቅብቅ ማለት፣ የጽሕፈት መፈልሰፍ፣ ተሞላ ጕደል ለአስተዳደሩ መቃናት በቋንቋ አማካይነት የተስተካከለ ግንኙነት የሚፈልገው የመንግሥት መመሥረት፣ ከዚህ ይበልጥ በቋንቋ አማካይነት ከፍ ያለ ግንኙነት የሚደረግበት መስፋፋት፣ የማተሚያ ቤቶች መቋቋም፣ የሥነ ጽሑፍ መዳበር፣ እኒህ ሁሉ ነገሮች በቋንቋ እድገት ውስጥ ታላላቅ ለውጦችን አምጥተዋል። እኒህም የተባሉት ነገሮች በሚካሄድበት ጊዜያት ነገዶችና ብሔረሰቦች እየፈለሱ ተበታትነዋል፣ ተደበላልቀዋል፣ ተዳቅለዋል፣ በኋላም ብሔራዊ ቋንቋዎችና መንግሥታት ተቋቋሙ፣ አብዮቶች ተካሄዱ፣ ነባር ሥርዐተ ማኅበሮችም ባዲስ ተተኩ፣ እኒህም ሁሉ ነገሮች በቋንቋ እድገት ውስጥ ለመጡ ታላላቅ ለውጦች ምክንያት ሆኑ።

ቋንቋ የሚያድገው እንደሉዓላዊ መዋቅሩ ሁሉ የነበረውን አጥፍቶ አዲስ በመገንባት ነው ማለት ትልቅ ስሕተት ነው። በውነቱ ቋንቋዎች ያሉትን ቋንቋዎች በማጥፋትና አዲስ ቋንቋዎችን በመፍጠር ሣይሆን የሚያድጉ ያሉትን ቋንቋዎች መሠረታውያን ነገሮች በማስፋትና በማደርጀት ነው። የአንድ ቋንቋም ካንድ ዐይነተኛ ለውጥ ወደ ሌላ መሸጋገር፣ በድንገት የሚያድግ የቆየውን ዐይነተኛ መልኩን ባንድ ጊዜ አጥፍቶ አዲስ በመፍጠር የሚደረግ ሣይሆን፣ የአዲሱ የቋንቋ መዋቅር የአዲሱ ዐይነተኛ የቋንቋ መልከ ነገሮች ዝግ ባለ ግን በማያቋርጥ ሁኔታ መደርጀትና የነባሩ ዐይነተኛ የቋንቋ መልከ ነገሮች ዝግ ባለ ግን በማያቋርጥ ሁኔታ መፍረስ መጥፋት ነው።

አንድ ቋንቋ ከቆየው ዐይነታዊ መልኩ ወደ አዲስ ዐይነታዊ መልኩ በሚሸጋገርበት ጊዜ የድንገተኛ ፍንደታን አስፈላጊነት ማርክሲዝም ስለሚያስገነዝብ፣ ቋንቋ የሚያድገው ደረጃ በደረጃ የሚባለው ሀሣብ ማርክሣዊ ሀሣብ ነው ይባላል። ግን ይህ እውነት አይደለም- በዚህ አባባልም ምንም ማርክሣዊ የሆነ ነገር አይገኝበትም። በቋንቋዎች የእድገት ታሪክ ውስጥ ድንገተኛ ፍንደታዎች አሉ የሚል ሀሣብ ሚዛን የሚያነሣ አይደለም። ማርክሲዝም በቋንቋዎች ዕድገት ውስጥ ድንተገኛ ፍንደትዎች፣ ማለትም የአንድ ነባር ቋንቋ ድንገተኛ ሞትንና የሌላ አዲስ ቋንቋ ድንገተኛ ልደት አይቀበልም። ላፋርግ በፈረንሣይ «ከ1789 — 1794 ድንገተኛ የቋንቋ አብዮት ነበር» ሲል ተሣስቷል። (የላፋርግን ፈረንሣይኛ ቋንቋ ከአብዮቱ በፊትና በኋላ የሚለውን ጽሑፍ ይመለከቷል።) በዚያን ጊዜ የፈረንሣይኛ ቋንቋ መድበለ ቃላት በአዳዲስ ቃላትና የአገላለጽ ዘዴዎች ዳብሮ ነበር። ከዚሁ ከመድበለ ቃላቱም ያረጁ ያፈጁ ቃላት ወጥተዋል። አንዳንድ ቃላትም የፊት ትርጕማቸውን ለውጠዋል። ግን ለውጡ ይህ ብቻ ነበር። እንዲህ ዐይነቱ

ለውጥም በምንም ዐይነት ያንድ ቋንቋን ዕድል አይወስንም። ባንድ ቋንቋ ውስጥ የሚገኘው ዋናው ነገር የሰዋሰው ስርዐቱና ነባሩና መሠረታዊው የመድበለ ቃላቱ ክፍል ነው። የፈረንሣይኛ ቋንቋ የሰዋሰው ስርዓትና ነባሩና መሠረታዊው የመድበለ ቃላት ክፍል በፈረንሣይ የከበርቴ አብዮት ዘመን መጥፋቱ ይቅርና ምንም ያህል ለውጥ ሣያሣይ እስከ ዛሬ ቆይቷል። አምስትና ስድስት ዓመት ላንድ ቋንቋ መጥፋትና ለሌላ አዲስ ብሔራዊ ቋንቋ መገንባት («ድንገተኛ የቋንቋ አብዮት» መሆኑ ነው ይሄ) እጅግ - በጣም እጅግ አጭር ጊዜ ነው። ለዚህ ዐይነቱ ለውጥ ምዕተ ዓመታት ያስፈልጋሉ።

ማርክሲዝም አንድ ቋንቋ ከቆየው ዐይነታዊ መልኩ ወደ አዲስ ዐይነታዊ መልኩ የሚሸጋገረው በድንተገኛ ፍንደታ ነው አይልም። ወይም አንድ ነባር ቋንቋ በድንገት ጠፍቶ በሌላ አዲስ ቋንቋ ይተካል ብሎም አያትት። አንድ ቋንቋ ከቆየው ዐይነታዊ መልኩ ወደ አዲስ ዐይነታዊ መልኩ የሚያደርገው ሽግግር፤ የአዲሱ ዐይነታዊ መልክ አንዳንድ ነገሮች በዝግታ በቋንቋው ውስጥ እየተጠራቀሙና የቆየው ዐይነታዊ መልኩ አንዳንድ ነገሮች እንዲሁ በዝግታ ከቋንቋው እየመነመኑና እየጠፉ በመሄዳቸው ነው።

የሽግግር ሕግ ከቆየው ዐይነተኛ መልክ ወደ አዲስ ዐይነተኛ መልክ ድንተተኛ ፍንደታ ነው የሚመጣ ብለው የሚያስቡ ጓዶች ሊያውቁት የሚገባው፤ ይህ ሀሣባቸው ለቋንቋ የዕድገት ታሪክ ብቻ ሣይሆን፤ በሌሎችም የኢኮኖሚያዊ ወይም የሉዓላዊ መዋቅሩ ጠባይ ባላቸው ማኅበራዊ ክስተቶች ላይም ሁልጊዜ የማይሠራ መሆኑን ነው። በተጻራሪ መደቦች ባልተከፋፈለ ማኅበረሰብ ውስጥ ግን ግድ አስፈላጊነት የለውም። በስምንትና በአሥር ዓመታት ውስጥ የሀገራችንን እርሻ ከከበርቴ ግለኛ - ጭሰኛ እርሻ ወደ ኅብረተሰባዊ የጋርዮሽ እርሻ ለውጠነዋል። ይህ የቆየውን ከበርቴያዊ የኢኮኖሚ ሥርዓት በገጠሩ ያጠፋና አዲስ ኅብረተሰባዊ ሥርዐት የፈጠረ አብዮት ነው። ይሁንና ይህ አብዮት በፍንደታ ማለትም ያለው የመንግሥት ኃይል በመገልበጡና አዲስ በመፈጠሩ የተደረገ አይደለም። በገጠሩ ከቀድሞው የከበርቴ ሥርዐት ወደ አዲስ ሥርዐት በተደረገ ዘገምተኛ ሽግግር እንጂ። ይህንም ማድረግ የተቻለው ከላይ የመጣ አብዮት በመሆኑ፤ ሥልጣን በያዘው ኃይል በመጀመሩና ባብዛኛው ገበሬ ድጋፍ በመከናወኑ ነው።

ቋንቋዎች ሲዳቀሉ ከቆየ ዐይነተኛ መልክ ወደ አዲስ ዐይነተኛ መልክ በሚቀየር ድንገተኛ ሽግግር፤ በድንተት ፍንደታ አዲስ ቋንቋ ይፈጠራል። ይህንም ጉዳይ ካለፉት ታሪኮች ብዙ ምሣሌዎች ጠቅሶ ማረጋገጥ ይቻላል የሚሉ አሉ። ግን ይህም ስሕተት ነው።

የቋንቋ መዳቀል በጥቂት ዓመታት ውስጥ ለውጥ እንደሚያመጣ ኃይል መቆጠር የለበትም። የቋንቋ መዳቀል ረዥም ጊዜ የሚወስድ ለብዙ ምዕተ ዓመታት የሚቀጥል ነገር ነው። ይህም በመሆኑ ቋንቋዎች ሲዳቀሉ በፍንደታ አዲስ ቋንቋን ይፈጥራሉ የሚለው ሐሣብ የተሳሳተ ነው።

በተጨማሪም በቋንቋዎች- እንበል በሁለት ቋንቋዎች መዳቀል ጊዜ ሁለቱን ተዳቃይ ቋንቋዎች የማይመስል በዐነተኛ መልኩም ከነሱ የሚለይ አዲስ ሶስተኛ ቋንቋ ይፈጠራል ማለት ትክክል አይደለም። በእርግጥ ከተዳቃዮቹ ውስጥ አንዱ ቋንቋ አሸንፎ ይወጣል። የሰዋስው

ስርዐቱንና ነባሩንና መሠረታዊውን የመድበለ ቃላቱን ክፍል እንዳለ ጠብቆ ይቆያል። የውስጣዊ ዕድገት ሕግጋቱ በሚፈቅድለትም መጠን ማደጉን ይቀጥላል። በዚህም ጊዜ ሌላኛው ቋንቋ ቀስ በቀስ ዓይነታዊ መልኩን እያጣ ይሄድና ይሞታል።

ከላይ እንዳየነው የሁለት ቋንቋዎች መዳቀል አዲስ ሶስተኛ ቋንቋን አያስገኝም። አንደኛው ቋንቋ ይዘልቃል። ሰዋሰዋዊ ሥርዐቱና ነባሩንና መሠረታዊውን የመድበለ ቃላቱን ክፍል ያቆያል። ውስጣዊ የእድገት ሕግጋቱም በሚፈቅድለት መጠን ያድጋል።

በሚዳቀሉ ጊዜ የአሸናፊው ቋንቋ መድበለ ቃላት በተሸናፊው ቋንቋ መድበለ ቃላት ይበለጽጋል። ይህ ግን ቋንቋውን ያጠናክረዋል እንጂ አያደክመውም።

የሩስያ ቋንቋ ይህንኑ ዐይነት ዕድል ገጥሞታል። በታሪክ የዕድገት ግሥጋሴ ውስጥ የሌሎች ብሔራት ቋንቋዎች ተዳቅለውት ሁልጊዜም አሸናፊ ሁኖ ወጥቷል።

በሚዳቀሉም ጊዜ የሩስያ ቋንቋ መድበለ ቃላት በሌሎች ቋንቋዎች ቃላት ሠፍቷል። ግን ይህ የሩስያን ቋንቋ አላደከመውም። እንዳውም ይበልጥ አበልጽጐታል። ይበልጥ አጠንክሮታል።

የሩስያ ቋንቋ በልዩ ብሔራዊ የግል መልኩ በኩል ጥቂትም አልተጐዳ። የዚህም ምክንያቱ የሰዋሰው ስርዓቱንና ነባሩንና መሠረታዊውን የመድበለ ቃላቱን ክፍል በመጠበቁና የዕድገቱ ውስጣዊ ሕግጋትም በሚፈቅድለት መጠን መራመዱንና መሻሻሉን በመቀጠሉ ነው።

ጓዶች የሠነዘሩት ትክክል ያልሆነ የመዳቀል ሀሣብ ለሶቭዬት ሥነ ቋንቋ ምንም ጥቅም አይሰጠውም። ዋናው የሥነ ቋንቋ ጥናት የቋንቋን እድገት ውስጣዊ ሕግጋት ማጥናት እንዲሁ እውነት ነው። ስሕተተኛው የማዳቀሉ ሀሣብ ሠንዛሪዎች ግን ይህን መሥራት ቀርቶ ለመሥራትም እንዳልቃጡ መታወቅ አለበት። - አልታያቸውም ወይም አልገባቸውም።

ጥያቄ፤ በቋንቋ ችግሮች ላይ ፕራቭዳ ግልጽ ውይይት መክፈቱ ትክክል ነው?

መልስ፤ አዎን፤ ትክክል ነው።

የቋንቋ ችግሮች በምን መንገዶች መታየት እንዳለባቸው በዚህ ውይይት ማክተሚያ ላይ ግልጽ ይሆናል። ውይይቱ ጠቃሚ መሆኑን ግን ካሁኑም መናገር ይቻላል።

በመጀመሪያ ነገር በየቦታው ባሉ የቋንቋ ጥናት አካባቢዎች ለሣይንስና ለሣይንስ ሊቃውንት እንግዳ የሆኑ ነገሮች መፈጠራቸውን ውይይቱ ጠቁሟል።

በሶቭዬት ሥነ ቋንቋ ውስጥ ያሉ ጉዳዮችን በጥቂቱም እንኳን ቢሆን መተቸት፤ ሌላው ቀርቶ አለ በተባለው «አዲስ ትምህርት» ላይ በጥቂቱ እንኳን ትችት ለመሠንዘር መሞከር በዋናዎቹ የቋንቋ ጥናት አካባቢዎች የማይፈቀድ ጉዳይ ሁኗል። የኤንዋይማርን ትምህርቶች ለመተቸት በመሞከራቸው ወይም በትንሹም እንኳን ቢሆን በመቃወማቸው ብርቱ የቋንቋ ሠራተኞችና ተመራማሪዎች ከሥራቸው ተባረዋል ወይም ተሽረዋል።

አንዳንድ የቋንቋ ሊቃውንትም በሥራቸው ፍሬያማነት ሳይሆን የኤንዋይማርን ሃሳቦች በጅምላ በመቀበላቸው ብቻ በከፍተኛ ቦታዎች ላይ ተሹመዋል።

ምንም ዐይነት ሣይንስ ያለ ሃሳብ ግጭትና ያለ ትችት ነጻነት እንደማያድግና እንደማይለመልም የታወቀ ነገር ነው። ይህ ቁም ነገር ግን በሚያሣዝን ሁኔታ ተንቋል፤ ተጥሷል። ምንም ስሕተትን አንፈጽምም የሚሉ፤ ምንም ዐይነት ትችት ከመቀበል ራሣቸውን ያገለሉ፤ ራሣቸው ሕግ ሁነው ያሻቸውን የሚሠሩ መሪዎች ተነሥተዋል።

አንድ ምሣሌ እሰጣለሁ። «የባኩ ኮርስ» የሚባለው (ኤንዋይማር በባኩ ይሰጠው የነበረውን ትምህርት) ራሱ ደራሲው እንደገና እንዳይታተም ያደረገውን የከለከለውን ኮስር እኒህ መሪዎች (ጓድ ሚሾካኒኖብ የኤንዋይማር «ደቀመዛሙርት» ይላቸዋል) እንደገና እንዲታተም ከማዘዛቸውም በላይ ያለ አንዳች ቅሬታም ለተማሪዎች በሚታዘዙ የጥናት መጻሕፍት ዝርዝር ውስጥ እንዲገባ አድርገዋል። ተማሪዎቹን የታገደ «ኮርስ» መጽሐፍ እንዲያነቡ ሲያደርጋቸው እንዳታለሏቸው ግልጽ ይኖናል። በጓድ ሚሾካኒኖብና በሌሎችም አንዳንድ የቋንቋ ምሁራን ቀናነት እርግጠኛ ባልሆን ኖሮ፤ ይህን ዐይነቱን ድርጊት ከአሻጥር እኩል በቆጠርኩት ነበር።

ይህ እንዴት ሊሆን ቻለ? ይህ ሊሆን የቻለው በቋንቋ ጥናት አካባቢዎች ውስጥ የተፈጠረው የፈላጭ ቆራጭነት አስተዳደር ሀላፊነት አልባ የሆነና ግለኛ እርምጃዎችን የሚያበረታ ስለሆነ ነው።

ውይይቱም እጅግ ጠቃሚ የሆነው በመጀመሪያ ነገር ይህን የፈላጭ ቆራጭነት አስተዳደር ስላጋለጠና ስለሰባበረው ነው።

የውይይቱ ጠቃሚነት ግን እዚህ ላይ አያበቃም። በዋናዎቹ የሥነ ቋንቋ ክበቦች ውስጥ ያሉትን በቋንቋ ዐቢይ ጥያቄዎች ላይ የተሰነዘሩትን ውዥንብራዊ ሀሣቦችንም አሣይቷል ውይይቱ እስከተጀመረ ድረስ የኤን ዋይ ማር «ደቀ መዛሙርት» ጭጭ ብለውና በሥነ ቋንቋ ውስጥ ያለውን አጥጋቢ ያልሆነ ሁኔታ ደበስበስ አድርገው አልፈውት ነበር። ውይይቱ ሲጀመር ግን ዝም ማለት አልተቻላቸውም። ሀሣባቸውን በጋዜጦች ላይ እንዲገልጹ ተገደዱ። እና ውጤቱ ምን ሆነ? በኤን ዋይ ማር ትምህርቶች ውስጥ አያሌ ጉድለቶች፤ ስሕተቶች፤ በወጉ ያልተገለጹ ችግሮችና እጅግ ንድፋዊ የሆኑ ሀሣቦች እንዳሉባቸው ተገለጸ። ለምንድነው የኤን ዋይ ማር «ደቀ መዛሙርት» አሁን ውይይቱ ከተጀመረ በኋላ በኒህ ነገሮች ላይ መናገር የጀመሩት ብሎ መጠየቅም ይቻላል። ለምን መጀመሪያ ነገሩን አልመረመረሩትም? ለምንድን አንድ የሣይንስ ሊቅ ማድረግ እንደሚገባው ነገሩን በጊዜው በግልጽና በቀጥታ አልተነጋገሩበትም?

የኤን ዋይ ማር «አንዳንድ» ስሕተቶች «ደቀመዛሙርቱ» ከተገነዘቡ በኋላ እኒህ «ደቀመዛሙርት» የሶቭዬት ሥነ ቋንቋ ሊያድግ የሚችለው ማክሣዊ ናቸው በሚሏቸው በኤንዋይማር «የተቃኑ» ትምህርቶች መሠረት ላይ ነው ብለው ያስባሉ። የለም ከኤ ንዋ ይማር «ማርክሲዝም» ስ አድኑን! እርግጥ ኤንዋይማር ማርክሣዊ ለመሆን ፈልጐም ሞክሮም ነበር፤ ግን አልተሣካለትም።

ኤን ዋይ ማር በሥነ ቋንቋ ውስጥ ትክክል ያልሆነውንና ኢማርክሣዊ የሆነውን ቅርጸ ሐሣብ ማለትም ቋንቋ ሉዓላዊ መዋቅር ነው እሚል ውዥንብራም ሀሣብ ውስጥ ገብቶ ሥነ ቋንቋንም ውዥንብር ውስጥ ከቶት ነበር። የሶቭዬት ሥነ ቋንቋ በተሣሣተ ቅርጸ ሀሣብ መሠረትነት ወደ ፊት ሊራመድ አይችልም። በተጨማሪም ኤን ዋይ ማር የቋንቋን «የመደብ ጠባይ» በሚመለከት ረገድ ሌላ የተሣሣተና ኢማርክሣዊ የሆነ ቅርጸ ሀሣብ በሥነ ቋንቋ ውስጥ በማስገባት ራሱንና ሥነ ቋንቋውን ውዥንብር ውስጥ ጣለው። የሶቭዬት ሥነ ቋንቋ ለሕዝቦችና ቋንቋዎች ታሪክ ጠቅላላ ጉዞ ተጻራሪ በሆነ የተሣሣተ ቅርጸ - ሀሣብ መሠረት ላይ ሊራመድ አይችልም።

ኤን ዋይ ማር በጠብራራነት በጉራና በትዕቢት፤ ደፋርና ያልተጠና ቅዋሜን ከሱ ፊት በተሠሩ የሥነ ቋንቋ ሥራዎች ላይ ሁሉ ሠነዘረ።

ኤን ዋይ ማር በሥነ ቋንቋ ውስጥ ያለን የአወዳዳሪ - ታሪካዊ አጠና ዘዴን ቅጥባጣ መንገድ «ሀሣባዊ» ነው ሲል ነቀፈ። ይሁንና አንዳንድ ቀርነቶች ቢኖሩበትም እንኳን፤ የአወዳዳሪ - ታሪካዊ የአጠናን ዘዴ በእርግጥ ከኤንዋይ ማር ሀሣባዊ አራት ነገሮች ትንተና የተሻለ ነው። ምነው? የአወዳዳሪ - ታሪካዊ የአጠናን ዘዴ ሥራት፤ የቋንቋ ጥናትን ሲያበረታታ የኤን ዋይ ማር አራት ነገሮች ትንተና ግን በሶፋ ላይ ተጠቅሎ በዝነኞቹ የአራቱ ነገሮች የሻይ ብርጭቆ ውስጥ ዕድልን ወደ መተንበይ (ወደ መጠንቆል) የሚገፋፋ በመሆኑ።

ኤን ዋይ ማር የቋንቋ ቤተሰቦችን ማጥናት «የቋንቋ ነቅዐ - ዘር መላምት አንድ መልክ ነው ሲል በትዕቢት ተቃውሞታል። ይሁንና እንደ እስላቭ ብሔሮች ያሉ ብሔሮች የቋንቋ መቀራረብ የማይጠረጠር ነገር ነውና እኒህን ብሔሮች የቋንቋ መቀራረብ የማይጠረጠር ነገር ነውና የኒህን ብሔሮች የቋንቋ መቀራረብ ማጥናት በሥነ ቋንቋ ውስጥ ላለ የቋንቋ ዕድገት ሕግጋት ጥናት ትልቅ ጥቅም ይሰጣል። «የቋንቋ ነቅዐ - ዘር» መላምት ከዚህ ጋር ምንም ግንኙነት የለውም።

ኤን ዋይ ማርን በተለይም «ደቀመዛሙርቱን» የሚያዳምጥ ሰው ከኤን ዋይ ማር በፊት የቋንቋ ጥናት እንዳልነበረና የቋንቋ ጥናት የተጀመረው በኤንዋይማር «አዲስ ትምህርት» ነው ብሎ ተማሰብ ይደርሳል። ከዚህ ሰው (ከኤን ዋይ ማር) ይልቅ ማርክስና ኤንግልስ እጅግ በጣም ትሁቶች ነበሩ። የዲያሌክቲካዊ ቁስ አካል ፍልስፍናቸው ያለፉ ዘመናት ሣይንሶችና ፍልስፍና እድገት ውጤት እንደነበር ገልጸዋል።

ስለዚህ ውይይቱ በሶቭዬት ሥነ ቋንቋ ውስጥ ያሉትን የርእዮተ ዓለም ቀርነቶችም ስላጋለጠ በጣም ጠቃሚ ነው።

በአፋጣኝ የኤን ዋይ ማር ስሕተቶች ከሥነ ቋንቋችን ከተወገዱ፤ ሥነ ቋንቋችን አሁን ካለበት ችግር በአፋጣኝ ሊላቀቅ ይችላል።

የሶቭዬት ሥነ ቋንቋን በተደላደለ መሠረት ላይ ሊያውለው የሚችለው የፈላጭ ቆራጭነት አድሐሪ መንፈስ ከሥነ ቋንቋ ማጥፋት፣ የኤንዋይማርን ስሕተቶች ማስወገድ፣ ማክርሲዝምን በሥነ ቋንቋ ውስጥ ማስገባት ይመስለኛል።

ፕራቭዳ ፣ ሰኔ፣ 20፣ 1950

## አንዳንድ የሥነ ቋንቋ ችግሮችን በሚመለከት ጉዳይ ላይ።

ለጓድ ኢ. ክራሺኒንኮቫ ጥያቄዎች የተሰጡ መልሶች፡-

ጓድ ክራሺኒንኮቫ

ጥያቄዎችህን እንደሚከተለው እመልሣለሁ።

1. ጥያቄ፣ ጽሑፍዎ ቋንቋ የኢኮኖሚያዊ ወይም የሉዓላዊ መዋቅሩ ክፍል እንዳይደል በሚያሣምን ሁኔታ ያስረዳል። ታድያ ቋንቋ የሁለቱም ማለት የኢኮኖሚያዊውም የሉዓላዊ መዋቅሩም ክስተት ነው ብንል ያስኬዳል? ወይስ ቋንቋ በመሀል ያለ ክስተት ንወ ብንል ትክክል ይሆናል?

መልስ፣ እርግጥ ቋንቋ የማኅበረሰቡ ክስተት እንደመሆኑ፣ ሁሉም የማኅበረሰቡ ክስተቶች - ኢኮኖሚያዊውና ሉዓላዊ መዋቅሩም ጭምር የሚያሣዩት የወል የሆነ መልክ በውስጡ አለ። ይህም የወል የሆነ መልክ ማኅበረሰቡን ማገልገል ነው። ይህ ብቻ ነው በማኅበረሰብ ክስተቶች መሀል ያለ የወል መልክ። ከዚህ ያለፈ በማኅበረሰብ ክስተቶች መሀል ዋና ዋና ልዩነቶች አሉ። ይህም ማለት የማኅበረሰብ ክስተቶች ከወል መልካቸው ሌላ፣ አንዳቸውን ከሌላኛቸው የሚለያቸው፣ የራሣቸው የሆኑ፣ ለሣይንስ ተቀዳሚ ጥቅሞችን የያዙ ልዩ መልኮች አሏቸው። የኢኮኖሚያዊ መዋቅሩ መልኮች ማኅበረሰቡን በኢኮኖሚ በኩል በማገልገል ይጠቃለላሉ። የሉዓላዊ መዋቅሩ ልዩ መልኮች በፖለቲካ፣ በሕግ፣ በሥነ ኪነትና፣ በሌሎችም ሀሣቦችና በእኒህም ጋር በሚቋጩ የፖለቲካ፣ የሕግና የሌሎችም ተቋሞች አንጻር ማኅበረሰቡን ማገልገል ነው። ቋንቋንስ ከሌሎቹ ማኅበረሰባዊ ክስተቶች የሚለዩት ልዩ መልኮቹ ምንድን ናቸው? የቋንቋ ልዩ መልኮቹ የሚገለጹት በማኅበረሰቡ ውስጥ ማለትም በሰዎች ዘንድ የመገናኛ፣ የሀሣብ መለዋወጫና በሁሉም የሰዎች ክበበ ተግባር በምርት ሆነ በምርት ግንኙነት፣ በፖለቲካ ሆነ በባህል፣ በማኅበራዊ ሕይወት ሆነ በምርት ግንኙነት፣ በፖለቲካ ሆነ በባህል፣ በማኅበራዊ ሕይወት ሆነ በዕለት ውሎ፣ ሰዎች መግባባት እንዲችሉና የኅብረት ሥራቸውንም እንዲያቀናብሩ የሚያደርግ መሣሪያ በመሆኑና ማኅበረሰቡንም የሚያገለግለው በዚህ ረገድ በመሆኑ ነው። እኒህ የተባሉት ልዩ ልዩ መኮች የቋንቋ ብቻ ናቸው። የቋንቋም ልዩ መልኮች ብቻ በመሆናቸው፣ ቋንቋ ራሱን የቻለ ሳይንስ - ሥነ ቋንቋ - የሚያተኩርበት ጥናት ነው። ቋንቋ እንዲህ ያሉ ልዩ መልኮች ባይኖሩት ሥነ ቋንቋ ራሱን የቻለ ሣይንስ መሆኑ ይቀር ነበር።

ባጭሩ፣ ቋንቋ በኢኮኖሚያዊው ሆነ በሉዓላዊ መዋቅሩ ክፍል ውስጥ ሊጠቃለል አይችልም።

ቋንቋ በኢኮኖሚያዊውና በሉዓላዊ መዋቅሩ መሐል ላይ ያለ «መሐላይ» ክስተትም ውስጥ ሊጨመር አይችልም:: «መሐላይ» የሚባል ክስተት የለምና:: ምናልባት ቋንቋ ከማኅበረሰቡ የምርት ኃይላት ክፍል፤ ለምሣሌ የምርት መሣሪያዎች ውስጥ ሊጨመር ይችል ይሆን? እርግጥ በቋንቋና በምርት መሣሪያዎች መሐል ተመሣሣይነት አለ:: ይኸውም የምርት መሣሪያዎች - እንደ ቋንቋ ሁሉ - ግድየለሽነት የማሣየትና የቀድሞውንና አዲሶቹን የማኅበረሰብ መደቦችን በእኩል የማገልገል ጠባይን ያሳያሉ:: ሆኖም ቋንቋን በምርት መሣሪያዎች ክፍል ውስጥ ለመጨመር ይህ ምክንያት ሊሆን አይችልም::

አንድ ጊዜ ኤን ዋይ ማር «ቋንቋ በኢኮኖሚያዊው መዋቅር ላይ ያለ ሉዓላዊ መዋቅር ነው» የሚለውን ሀሣቡን ቅዋሜ እንደ ተነሣበት ባወቀ ጊዜ፤ ሀሣቡን «አቃንቶ» «ቋንቋ የምርት መሣሪያ ነው» ብሎ ነበር:: ግን ይህ ትክክል አልነበረም::

የቋንቋና የምርት መሣሪያዎች ተመሣሣይነት ፊት የጠቀስኩት ብቻ ነው:: ይሁንና በሌላ በኩል በቋንቋና በምርት መሣሪያዎች መሀል ትልቅ ልዩነት አለ:: ይኸውም የምርት መሣሪያዎች ቁስ ሐብትን ሲያመርቱ ቋንቋ ምንም አያመርትም:: ያመርታል ቢባል እንኳ ቃላትን ብቻ ነው:: የምርት መሣሪያዎች ያሏቸው ሰዎች ቁስ ሐብትን ሊያመርቱ ይችላሉ:: ግን እኒሁ ሰዎች ቋንቋ ቢኖራቸውና የምርት መሣሪያዎች ባይኖራቸው ቁስ ሃብትን ሊያመርቱ አይችሉም:: ቋንቋ ቁስ ሐብትን ለማምረት የሚያስችል ቢሆንማ ወሬኞች በዓለም ያሉ ሀብታሞች በሆኑ ነበር::

2. ጥያቄ፤ ማርክስና ኤንግልስ ቋንቋ «የሐሳብ የቅርብ እውነታ» «ተግባራዊ ....እውነተኛው ንቃት» ነው ይላሉ:: «ሀሣብ» ይላል ማርክስ፤ «ከቋንቋ ተነጥሎ የሚገኝ ነገር አይደለም» በርስዎ ሀሣብ፤ ሥነ ቋንቋ ስለ ቋንቋ ይዘተ ሀሣብ ምን ያህል መጠበብ አለበት? ሥነ ይዘተ - ሀሣብ፤ ታሪካዊ ሥነ ይዘተ ሀሣብ፤ ሥነ ይትበሀል፤

ወይስ ቅርጽ ብቻ ላይ ሥነ ቋንቋ ያተኩር?

መልስ፤ ሥነ ይዘተ - ሀሣብ ከሥነ ቋንቋ ዋና ዋና ቅርንጫፎች አንዱ ነው:: የቃላት የሀሣብ ይዘትና የአገላለጽ ዘዬዎች በቋንቋ ጥናት ውስጥ ከፍ ያሉ ነገሮች ናቸው:: ስለዚህ፤ ሥነ ይዘተ - ሀሣብ በሥነ ቋንቋ ውስጥ የጠበቀ ቦታ አለው::

ይሁንና የሥነ ይዘተ - ሀሣብን ጥያቄዎች ስንሰራና በስብስብ ማስረጃዎቹ ስንጠቀም አስፈላጊነቱን እንዳናጋንንና ይልቁንም እንዳናወላግደው ያስፈልጋል:: አንዳንድ ስለ ሥነ ይዘተ - ሀሣብ የናረ ፍቅር ያላቸው የሥነ ይዘተ - ሀሣብ ሊቃውን፤ ቋንቋ «የሀሣብ ቅርብ እውነታ» ና ከማሠብ የማይለያይ መሆኑን ይዘነጋሉ:: ማሰብን ከቋንቋ አፋተው የቋንቋም ታሪክ ዕድሜው እንዳከተመና ያለ ቋንቋ መኖርም እንደሚችል ይናገራሉ::

ለምሣሌ ኤን ዋይ ማር እንዲህ ይላል፤

«ቋንቋ ልኖር የሚችል በድምጾች እስከተለጸ ብቻ ነው። የማሰብ ክንዋኔ በድምጽ ሣይገለጽ ይኖራል።.....ቋንቋ (በድምጽ የሚገለጸው) አዲስ ለመጡት ኀዋውን (ጠፈርን) እንደልባቸው ለሚመረምሩ ፍልስፎች ተግባሩን እየለቀቀ ነው። ማሰብ ቀድሞ ያለ ጥቅም ከቀሩት ስብስቦቹና ከአዲስ ተገኘቶዎቹ እየተለያየና ቋንቋን ገፍትሮ ሙሉ በሙሉ ቦታውን ሊወስድ ወደ ላይ እያደገ በሚሄድበት ጊዜ። የወደፊት ቋንቋ ከተፈጥሮ ጉዳዮች ነጻ በሆነ መንገድ በቴክኒክ የሚያድግ ማሰብ ይሆናል። ምንም ቋንቋ - ከተፈጥሮ አቋሞች ጋር ግንኙነት ያለው የንግግር ቋንቋ እንኳን - ይህን ሊያግደው አይችልም።»

(ምርጥ ሥራዎች - በኤን ዋይ ማር - ተመልከት)

ይህን «ሥራ - ምትሀት» መቀባጠር በቀላል ቋንቋ ብንተረጉመው፤ እንዲህ ያለ መደምደሚያ ማውጣት ይቻላል።

ሀ/ ኤን ዋይ ማር ማሰብን ከቋንቋ ያለያየዋል።

ለ/ ኤን ዋይ ማር በሰዎች መሀከል ከቋንቋ «የተፈጥሮ ጉዳዮች» ነጻ በሆነ «በተፈጥሮ አቋም» በተላቀቀ በማሰብ እርዳታ ብቻ ያለ ቋንቋ ግንኙነት ሊኖር ይችላል ይላል።

ሐ/ ማሰብን ከቋንቋ በመገንጠልና ከቋንቋ «የተፈጥሮ ጉዳዮች» ቋንቋን «ነጻ በማውጣት» ኤን ዋይ ማር በሀሣባዊነት አረንቋ ውስጥ ይወድቃል።

በሰው አእምሮ ውስጥ ሀሣብ በንግግር ከመገለጹ በፊት ያለ ቋንቋ ነገር፤ ያለ ቋንቋ ሽፋን ማለት በባዶ ቅርጹ ብቻ ይገኛል ተብሏል። ይህ ግን ሙሉ በሙሉ ስሕተት ነው። በምንም ጊዜ በሰዎች አእምሮ ውስጥ ያለ ምንም ዐይነት ሀሣብ የሚገኝ በቋንቋ ነገር፤ በቃላትና ሐረጐች መሠረት ብቻ ነው። ከቋንቋ ነገሮች ከቋንቋ «ተፈጥሮ ጉዳዮች» የተለየ ባዶ ሀሣብ የለም። «ቋንቋ የሀሣብ የቅርብ እውነታ ነው»። (ማርክስ) የሀሣብ እውነታ በቋንቋ ነው የሚገለጸው። ሀልዮታውያን ብቻ ናቸው ማሰብ ከቋንቋ የ «ተፈጥሮ ጉዳዮች» ያልተያያዘ ነው የሚሉና ያለ ቋንቋ ማሰብ ይቻላል ብለው የሚናገሩ።

ባጭሩ፤ ሥነ ይዘተ - ሀሣብን ማጋነንና ማወናከር ኤን ዋይ ማርን ወደ ሀሣባዊነት መራው።

ሥነ- ይዘተ - ሀሣብ ኤን ዋይ ማርና አንዳንድ «ደቀ መዛሙርቱ» ከፈጸሙት ማጋነንና ማወናከር ከተጠበቀ ለሥነ ቋንቋ በጣም ጠቃሚ ነገር መሆን ይችላል።

3 ጥያቄ፤ የከበርቴውና የወዝ አደሩ ሀሣቦች፤ ጽንሰ ሀሣቦች፤ ባህሎችና የሞራል ጉዳዮች ሁሉ በቀጥታ የሚቃረኑ ነገሮች እንደሆኑ ከዚህ በፊት የተናገሩት ትክክል ነው። የኒህ ክስተቶች መደባዊ መልክ በእርግጥ በቋንቋ ይዘተ - ሀሣብ (አንዳንዴም በቅርጹ - በመድበለ ቃላቱ - በትክክል በጽሑፍዎ ውስጥ እንደተገለጸው) ውስጥ ይንጸባረቃሉ። ተጨባጭ የሆኑ የቋንቋ ነገሮችን በመጀመርያም የቋንቋን ይዘተ - ሀሣብ ስንተነትን በቋንቋ ስለሚገለጹት ጽንሰ ሐሳቦች መደባዊ መልክ መናገር እንችላልን? በተለይም ቋንቋ የሚገልጠው የአንድን ሰውን

ሀሣብ ብቻ ሣይሆን ሰውየው ስለ እውነታ ያለውን ሀሣብም ጭምር በሚሆንበትና የመደብ ዝንባሌው እጅግ ግልጽ ሁኖ በሚታይበት ጊዜ?

መልስ፣ ባጭሩ ማወው የፈለከው፣ መደቦች ቋንቋ ላይ ተጽዕኖ ሊያሳድሩ ይችሉ እንደሆነ የራሣቸውን ቃላትና የአገላለጽ ዘዬ ባሉበት መደብ የተነሣ የተለያዩ ትርጉሞች የሚሰጡበት ጊዜ ያለ እንደሆነ ነው።

አወን መደቦች በቋንቋ ላይ ተጽዕኖ አላቸው። ባንድ ቋንቋ ውስጥ የራሣቸውን ቃላትና የአገላለጽ ዘዬዎች ያስገባሉ። አንዳንድ ጊዜም ላንድ ቃል ወይም ላንድ የአገላለጽ ዘዬ የተለያዩ ትርጉሞች ይሠጣሉ። ይህ የማይጠረጠር ነገር ነው።

ይህ ማለት ግን አንዳንድ የተለያዩ ቃላትና የአገላለጽ ዘዬዎች፣ እንዲሁም በይዘተ - ሀሣቡ ላይ ያሉ ልዩነቶች ላንድ ሕዝብ የጋራ በሆነ ቋንቋ እድገት ላይ ከፍ ያለ አገልግሎት አላቸው፣ ወይም ጥቅሙን ይቀንሣሉ፣ ጠባዩን ይለውጣሉ ማለት አይደለም።

መጀመርያ ነገር፣ እኒህ የተባሉት የተለዩ ቃላትና የአገላለጽ ዘዬዎች የይዘተ - ሀሣብም ልዩነቶች እጅግ ጥቂት በመሆናቸው የአንድ ቋንቋ አንድ መቶኛ እንኳን አይሆኑም። ስለሆነም የተቀሩት አብዛኞቹ ቃላትና የአገላለጽ ዘዬዎችና ይዘተ ሀሣባቸው ባንድ ማኅበረሰብ ውስጥ ላሉ ሁሉም መደቦች የጋራ ይሆናሉ። ሁለተኛ ነገር የመደብ መልክ ያላቸው የተለያዩ ቃላትና የአገላለጽ ዘዬዎች በንግግር ውስጥ በሚገቡበት ጊዜ በሌለ «የመደብ» ሰዋስው ሥርዓት ሣይሆን፣ ባለው የሁሉም ሕዝብ የጋራ በሆነው ቋንቋ የሰዋሰው ሥርዐት አማካኝነት ነው።

ስለዚህ፣ የአንዳንድ የተለዩ ቃላትና የአገላለጽ ዘዬዎች መኖርና ባንዳንድ ቃላት ላይ የሚታዩ የይዘተ - ሀሣብ ልዩነቶችም፣ ለሁሉም ሕዝብ የወል የሆነን የአንድ ቋንቋን መኖርና አስፈላጊነት የሚያስክድ ሣይሆን እንዳውም የሚያሣምን ነገር ነው።

4 ጥያቄ፣ በጽሑፍዎ ውስጥ ኤን ዋይ ማር ማርክሲዝምን ባካይ እንደሆነ በትክክል ገምግመውታል። ግን ይህ ማለት የሥነ ቋንቋ ሰዎች - እኛን ወጣቶቹን ጨምሮ - የማርን የሥነ ቋንቋ ቅርስ፣ ሆነም ቀረም ብዙ ጠቃሚ የሥነ ቋንቋ ምርምሮችን (ጓድ ቺኮባቫ፣ ሣንዚየቭና ሌሎችም በውይይቱ ጊዜ የጠቀሷቸውን) በሙሉ መተው አለብን ማለት ነው? የኤን ዋይ ማርን ሥራዎች በሂስ ዓይን ገምግመን ጠቃሚና ዋጋ ያለውን መውሰድ አንችልም?

መልስ፣ እርግጥ የኤን ዋይ ማር ስሕተቶች ሙሉ በሙሉ ስሕተቶች አይደሉም። ኤን ዋይ ማር ከፍ ያሉ ስሕተቶችን የፈጸሙ ማርክሲዝምን በተዛባ መንገድ ሥነ ቋንቋ ውስጥ ባስገባ ጊዜና ስለ ቋንቋ የግሉን ኤን ዋይ ማር የፈለሰማቸውን መላምቶች ትቶ በጥንቃቄና በዘዴ የተለያዩ ቋንቋዎችን የመረመረባቸው ጥሩና በሚገባ የተጻፉ ሥራዎች አሉት። በኒህ ሥራዎች ውስጥ ብዙ ጠቃሚና ትምህርታዊ ነገሮች ከኤን ዋይ ማር መውሰድና በአገልግሎት ላይ መዋል አለባቸው።

5 ጥያቄ፤ ብዙ የሥነ ቋንቋ ሊቃውንት ቅርጻዊነት የሶቭዬት ሥነ ቋንቋን ከኮደኮዱት ዋና ዋና ምክንያቶች አንዱ ነው ይላሉ። በሥነ ቋንቋ ውስጥ ቅርጻዊነት ምን እንደሆነና እንዴትስ ድል ሊመታ እንደሚቻል ያሉትን ሀሣብ ቢያስረዱን በጣም እንወድ ነበር።

መልስ፤ ኤን ዋይ ማርና «ደቀ መዛሙርቱ» የኤን ዋይ ማርን» አዲስ ትምህርት» ያልተቀበሉትን የሥነ ቋንቋ ባለሙያዎችን ሁሉ በ «ቅርጻዊነት» ይወነጅሏቸዋል። ይህ መቼም ቁም ነገርም፤ ብልሀትም አይደል።

ኤን ዋይ ማር ሰዋሰው ባዶ «ቅርጻዊነት» እንደሆነና የሰዋሰው ሥርዓትን የቋንቋ መሠረት የሚያደርጉ ቅርጻውያን ናቸው ይላል። ይህ መቼም ሞኝነት ነው።

በ «አዲሱ ትምህርት» ደራስያን ቅርጻዊነት የተፈለሰመው ካንዳንድ የሥነ ቋንቋ ባለሙያዎች ጋር የሚያደርጉትን ትግል እንዲያቃናላቸው ይመስለኛል።

የሶቭዬት ሥነ ቋንቋን ባለበት እንዲሄድ ያደረገው ኤን ዋይ ማርና «ደቀ መዛሙርት» የፈለሰሙት «ቅርጻዊነት» አይደለም። በሥነ ቋንቋ ውስጥ ያለ የኤን ዋይ ማር «ደቀ መዛሙርት» የፈላጭ ቆራጭነት አስተዳደርና በመላምቶች መሐል ያለ ገዋ እንጂ። በሥነ ቋንቋ ውስጥ ያለውን ውዥንብር አምጭዎቹ ኤን ዋይ ማርና የቅርብ ጓዶቹ ናቸው። የሥነ ቋንቋን ባለበት መሄድ ለመግታት አንዱም ሌላውም መጥፋት አለባቸው። በሶቭዬት ሥነ ቋንቋ ውስጥ ያሉን እኒህን ቀርነቶች ማስወገድ የሶቭዬት ሥነ ቋንቋን ጤናማ የሚያደርገውና በዓለም ሥነ ቋንቋ ውስጥ ቅድሚያ ቦታ እንዲኖረው ወደ ሚያስችለው ሰፊ ጥርጊያ የሚመራው ነገር ይሆናል።

ሰኔ 29 ቀን 1950

ፕራቭዳ ሐምሌ 4 ቀን 1950

## ለጓዶች የተሰጡ መልሶች።

ለጓድ ሣንዚየቭ፤

ደብዳቤህ ከማዕከላዊ ኮሚቴ የተሰጠኝ ገና ትላንት ስለ ነበረ ይህን መልስ ስጽፍልህ በጣም ከዘገየ በኋላ መሆኑ ነው።

በቋንቋ ዘዬዎች ላይ ስላለኝ አስተያየት ያቀረብካቸው ግምገማዎች ፍጹም ትክክል ናቸው።

የ «መደብ» የቋንቋ ዘዬዎች ሰፊውን ሕዝብ ሣይሆን ጥቂቱን የላይኛውን ክፍል ነው የሚያገለግሉ። ከዚህም በላይ የራሣቸው የሆነ የሰዋሰው ሥርዐት ወይም መሠረታዊ የቃላት ስብስብ የላቸውም። በዚህ አስተያየት የተለያዩ ራሣቸውን የቻሉ ቋንቋዎች ሁነው ሊያድጉ አይችሉም።

በሌላ በኩል፤ ሥፍራዊ የቋንቋ ዘዬዎች አብዛኛውን ሕዝብ ያገለግላሉ። የራሣቸውም የሰዋሰው ሥርዐቶችና መሠረታዊ የቃላት ስብስብ አላቸው። ነገሩን በዚህ አንጻር ስናየው፤ አንዳንድ ሥፍራዊ የቋንቋ ዘዬዎች፤ በብሔሮች መፈጠር ጊዜ የብሔሮች ቋንቋዎች መሠረት ሊሆኑና ራሣቸውን ወደቻሉ የብሔር ቋንቋዎች ሊያድጉ ይችላሉ። የሩስያ ብሔራዊ ቋንቋ መሠረት የሆነው የሩስያ ቋንቋ ይርኩሩስክ-ኦሬል የቋንቋ ዘዬ (የኩሩስክ-ኦሬል የንግግር ፈሊጥ) እንደ ምሣሌ ሊጠቀስ ይችላል። የዩክሬንያ ብሔራዊ ቋንቋ መሠረት የሆነው የዩክሬንያ ቋንቋ የፖልታሻ ኪብ የቋንቋ ዘዬም ሌላው ምሣሌ ነው። የኒህ ቋንቋዎች ሌሎች የቋንቋ ዘዬዎች ወጥነታቸውን አጥተው፤ ከቋንቋዎቹ ጋር ተዋህደው ጠፍተዋል።

የዚህ ተቃራኒ የሆነም ጉዳይ ሊፈጠር ይችላል። ለእድገት አስፈላጊው የኢኮኖሚ ሁኔታ በሌለበትና በዚህም ምክንያት ብሔር ሊሆን ያልበቃ ብሔረሰብ አንድ ቋንቋ በብሔረሰቡ መከፋፈል የተነሣ ሊጠፋ ይችላል። ባንዱ ቋንቋ ውስጥ አንድ ውህደትና መልክ ለማግኘት ጊዜ ያላገኙቱ የቋንቋው ሥፍራዊ የቋንቋ ዘዬዎችም ራሣቸውን የቻሉ የተለያዩ ቋንቋዎች ተመሆን ይደርሣሉ። በሞንጐላውያን ቋንቋ የደረሰውም ይህ ሣይሆን አይቀርም።

ሐምሌ 11 ቀን 1950

ፕራብዳ፤ ነሐሴ 2 1950

ለጓድ ዲቤልኪንና ለጓድ ኤስ ፉረር፦

ደብዳቤዎቻችሁ ደርሰውኛል።

የናንተ ስሕተት ሁለት ነገሮችን ማማታታችሁና ለጓድ ክራሺንንኮቭ በሰጠሁት መልስ ውስጥ የተተቸውን ነገር ትታችሁ በሌላ ነገር መተካታችሁ ነው።

በዛ መልሴ ውስጥ ያነሣሁት ስለ ቋንቋና ሀሣብ ሲያወጣ፤ ቋንቋን ከሀሣብ ነጥሎ በሀልዮታዊነት አረንቋ ውስጥ ሰለ ወደቀው ኤን ዋይ ማር ነበር። ስለዚህ በመልሴ ውስጥ የጠቀስኩት መናገር ስለሚችሉ ጤነኛ ሰዎች ነበር። እንዲህ ዐይነቱ ሰዎች ዘንድ ሀሣብ ሊኖር የሚችለው በቋንቋ መሠረትነት ብቻ እንደሆነና መናገር በሚችሉ ሰዎች ዘንድ ሀሣብ ብቻውን ያለቋንቋ ሊኖር እንደማይችል ገልጬ ነበር።

ይህን ሀሣቤን እንደ መቀበል ወይም እንደ መንቀፍ ቋንቋ የሌላቸውን፤ በቋንቋ ሊጠቀሙ የማይችሉን፤ ሀሣባቸውም በቋንቋ ሊገለጥ የማይበቃውን ደንቆሮና ዲዳ የሆኑ ሰዎች በትችታችሁ ውስጥ አመጣችሁ። እናንተም እንደምትረዱት ይህ እኔ ያልመረመርኩት ልመረምረውም ይገባኝ ያልነበር ፍጹም የተለየ ነገር ነው። ሥነ ቋንቋ የሚያወሣው መናገር ስለሚችሉ ጤነኛ ሰዎች እንጂ የመናገር ችሎታ ስለሌላቸው ደንቆሮና ዲዳ ሰዎች ስላልሆነ የተተቸውን ጉዳይ ወደ ጐን ጥላችሁ ያልተተቸ ሌላ ጉዳይ ተካችሁ።

2 ከጓድ ቤልኪን ደብዳቤ መረዳት እንደሚቻለው ቤልኪን «የቃላት ቋንቋን» (የንግግር ቋንቋን) ከ «ከምልክት - ቋንቋ» (የ «እጅ» ቋንቋ - ይለዋል ኤን ዋይ ማር) ጋር በአንድ በእኩል ረድፍ

ያሰልፈዋል። የምልክት ቋንቋና የንግግር ቋንቋ እኩል ዋጋ ያላቸው ነገሮች እንደሆኑና፤ ትንት ማኅበረሰቡ የንግግር ቋንቋ እንዳልነበረውና በዚያን ጊዜ የምልክት ቋንቋ በኋላ የመጣውን የንግግር ቋንቋ ሚና ይጫወት እንደ ነበር ጓድ ቤልኪን ያትታል።

በእርግጥ ጓድ ቤልኪን እንዲህ የሚያስብ ከሆነ ክፉኛ ተሣሥቷል። ምን ጊዜም በሰዎች ዘንድ በበቂ የመገናኛ መሣሪያነቱ ሲያገልግል የኖረ የማኅበረሰቡ አንድ ቋንቋ፤ የንግግር ቋንቋ ወይም የቃላት ቋንቋ ብቻ ነው። ቋንቋ የሌለው ማኅበረሰብ እጅግ ወደ ኋላ የቀረ እንኳን ቢሆን-አይገኝም።

በአውስትራሊያኖችና ባልፈው ምዕተ ዓመት ከነበሩት ቴራዲል ፉጋንስ የበለጠ ጥንታዊ ጐሣ እንኳን ቢሆን የራሱን የንግግር ቋንቋ አጥቶ አያውቅም። በሰው ልጅ ታሪክ ውስጥ የሰው ልጆች ከእንስሳት እንዲለዩና በቀበሌ እንዲሰበሰቡ፤ የማሰብ ኃይላቸውን እንዲያዳብሩ፤ ማኅበራዊ ምርት እንዲያደራጁ፤ ከተፈጥሮ ኀይላት ጋር የተሣካ ትግል ገጥመው ዛሬ የደረሱበትን የሥልጣኔ ደረጃ እንዲቀዳጁ ከረዱ በኋላ ኀይላት አንዱ የንግግር ቋንቋ ነው።

በዚህ ረገድ የምልክት ቋንቋ እጅግ ድሀና ጠባብ በመሆኑ የተነሣ የሚሰጠው ጥቅም እምብዛም ነው። በእውነቱ ለመናገር ምልክት ቋንቋ ቋንቋም አይደል።

የንግግር ቋንቋ ባንድ ወይም በሌላ መንገድ ሊተካ የሚችል የቋንቋ ምትክ እንኳን አይደለም። የተወሰኑ አገልግሎቶች ያሉትና ሰው በንግግሩ ጊዜ ለሀሣቡ አጽንኦት ለመስጠት የሚጠቀምበት ተቀጥላ ነገር እንጂ። የጥንቱ የእንጨት ዶማና አንድ ዘመናዊ ትራክተር እንደማይወዳደሩ ሁሉ የምልክት ቋንቋና የንግግር ቋንቋም አይወዳደሩም።

3 እናንተ መጀመርያ ልታውቁ የፈለጋችሁት ስለ ደንቆሮ - ድዳ በሁለተኛም ደረጃ ስለ ሥነ ቋንቋ ችግሮች ነው። ብዙ ጥያቄዎችንም እንድታቀርቡልኝ የገፋፋችሁም ይህ ነው። ደግ - ከፈለጋችሁም መልሱ ይኸው። የደንቆሮ ዲዳዎች ሁኔታ ምድን ነው? የማሰብ ችሎታ አላቸው? ሀሣቦች በአእምሯቸው ውስጥ አሉ። እርግጥ ደንቆሮ - ዲዳዎች የንግግር ችሎታቸው ስለሌላቸው ሀሣባቸው በቋንቋ መሠረትነት ሊነቃ አይችልም። ግን ይህ ማለት የደንቆሮ - ዲዳዎች ሀሣቦች ዳቦና ከ «ከተፈጥሮ አቋሞች» (የኤን ዋይ ማር የአገላለጽ ዘዴ ነው ይህ!) ጋር ያልተያያዙ ናቸው ማለት ነው? የለም፤ ማለት አይደለም። የደንቆሮ - ዲዳዎች ሀሣቦች የሚነቁትና ሊኖሩም የሚችሉት፤ በማየት በመዳሰስ፤ በመቅመስና በማሽተት አባላተ ስሜታቸው መነሾ በገሀዱ ዓለም ነባራውያን ነገሮች እርስ በእርሣቸው ባላቸው ግንኙነት ላይ በየዕለቱ ኑሯቸው በሚፈጥሯቸው ተምሣሌቶች፤ ስሜቶችና ጽንሰ ሐሳቦች መሠረትነት ላይ ብቻ ነው። ከኒህ ተምሣሌቶች ስሜቶችና ጽንሰ ሐሳቦች ውጪ፤ ሀሣብ ባዶ ነው። ምንም ይዘት ምንም ህልውና የለውም።

ሐምሌ 22 1950

ፕራብዳ፤ ነሐሴ 2 1950

ለጓድ ኤ. ኮለፖብ፤

ደብዳቤህ ደርሶኛል።

ሥራ ስለበዛብኝ መልስ ሳልሰጥህ ዘገየሁ።

ደብዳቤህ በውስጠ ታዋቂነት ሁለት መነሻ ሀሣቦች አሉት። - አንደኛ፤ የአንድ ደራሲ ሥራ በሚጠቀስበት ጊዜ ጥቅሱ ከሚያትተው የታሪክ ዘመን ገንጥሎ መመልከት የሚቻል መሆኑን፤ ሁለተኛም የአንድ የታሪክ ዕድገት ዘመን የጥናት ውጤት የሆነውን የማርክሲዝም ቅርጸ ሃሣብ ለሁሉም የታሪክ ዕድገት ዘመናት ሊሠራ መቻሉንና መለወጥ እንደሌለበት ያወሣል።

እኒህ ሁለቱም መነሻ ሀሣቦች እጅግ ስሕተቶች ናቸው። አንዳንድ ምሣሌዎችን ለመጥቀስ፦

1 በ1840 ውስጥ ሞኖፖሊ ካፒታሊዝም ገና ባልነበረበት ዘመን፤ ካፒታሊዝም እስከዚያን ባልያዛቸው ሥፍራዎች በሚስፋፋበትና ተሞላ ጉደል ምንም ሣያግደው በሚያድግበትና ያልተስተካከሉ የዕድገት ሕግጋት ሙሉ በሙሉ ገና ባልሠሩበት ጊዜ፤ ማርክስና ኤልግልስ ኅብረተሰባዊ አብዮት ባንድ ሀገር ብቻ ድል ሊያገኝ እንደማይችልና ድል ሊያገኝ የሚችለው በሁሉም ወይም ባብዛኞቹ የሠለጠኑ ሀገሮች የጋራ ትግል ብቻ እንደሆነ ተናግረው ነበር። ይህም የማርክሣውያን መሪ ሀሣብ ሁኖ ቆይቶ ነበር።

ይሁና በሀያኛው ምዕተ ዓመት መጀመርያ ላይ በተለይም በአንደኛው የዓለም ጦርነት ጊዜ፤ ቅድሞ ሞኖፖሊ ካፒታሊዝም ወደ ሞኖፖሊ ካፒታሊዝም መለወጡ ለማንም ግልጽ በሆነ ጊዜ፤ አዳጊ የነበረው ካፒታሊዝም እየቀጨጨ እየተጠራሞተ በሄደ ጊዜ፤ የዓለምን ኢምፔሪያሊስት ግንባር የማይሻሩ ሕጸጾች ጦርነቱ በገለጠ ጊዜ፤ የለውጥ ያልተስተካከለ ሕግ የወዝ አደሩ አብዮት በተለያዩ ሀገሮች በተለያዩ ጊዜያት ሊጐለምስ እንደሚችል በቅድሚያ በተመነ ጊዜ፤ ሌኒን ከማርክስ መላምት በመነሣት በእድገት ታሪክ ውስጥ ሁኔታዎች ሊያገኝ እንደሚችልና በሁሉም ወይም ባብዛኞቹ የሠለጠኑ ሀገሮች ባንድ ጊዜ ይገኛል የተባለው ኅብረተሰባዊ አብዮት በኒህ በተባሉት አገሮች፤ አብዮት ባንድ ጊዜ ባንድ መንገድ ባለመገላበጡና ባለመብሰሉ ምክንያት እንደማይቻልና የጥንቱ የማርክስና የኤንግልስ ቅርጸ ሀሣብ ካዲሶቹ የታሪክ ሁኔታዎች ጋር እንደማይሄድ አስረዳ።

እዚህ ላይ በኅብረተሰባዊ አብዮት ድል ጥያቄ ላይ ሁለት የተለያዩ፤ የሚቃረኑ እንዲያውም አንዳቸው አንዳቸውን የሚገፉ ሀሣቦች እንዳገኘን ግልጽ ነው፡

የአንድ ጽሑፍ ፍሬ ነገሩን ሣይመረመሩ ከታሪካዊ ሁኔታዎች ገንጥለው ዝም ብለው ጥቅስ የሚያፍሱ አንዳንድ መጽሐፋው ያንና ቀኖናውያን ከላይ ከተሰጡት ሁለት ሀሣቦች አንደኛውን ፍጹም ስሕተት ሁለተኛውን ፍጹም ትክክልና ለእድገት ዘመናት ሁሉ የሚሠራ አድርገው ይቆጥሩት ይሆናል። ማርክሣውያን ግን እኒህ መጽሐፋውያንና ቀኖናውያን እንደተሣሣቱ በደንብ ያውቃሉ። እያንዳንዳቸው ለዘመናቸው ነውና የሚያገለግሉት ሁለቱም መልሶች ፍጹም ሣይሆኑ ትክክል እንደሆኑ በሚገባ ይረዳሉ። የማርክስና የኤንግልስ መልስ

ለቅድመ ሞኖፖሊ ካፒታሊዝም ዘመን ሲያገለግል የሌኒን መልስ ደሞ ለሞኖፖሊ ካፒታሊዝም ዘመን ያገልግላል።

2/ ኤንግልስ «ጸረ ዱሕሪንግ» በተባለው ጽሑፉ ውስጥ ከኅብረተሰባዊ አብዮት ድል በኋላ፤ መንግሥት ይጠፋል ይላል። በፓርቲያችን ውስጥ ያሉ መጽሐፋውያንና ቀኖናውያን ይህን ተመርኩዘው በሀገራችን ከኅብረተሰባዊ አብዮት ድል በኋላ መንግሥቱ በፍጥነት እንዲጠፋ፤ የመንግሥት አካሎች እንዲዘጉና ቋሚ ወታደር እንዲቀር ፓርቲው እርምጃ እንዲወስድ መጠየቅ ጀመሩ።

ይሁንና የጊዜያችንን የዓለም ሁኔታ ያጤኑ የሶቭዬት ማርክሣውያን በካፒታሊስት ከበባ ጊዜ፤ የኅብረተሰባዊ አብዮት ባንድ ሀገር ድል ቢያገኝም ቅሉ፤ በሌሎች ሀገሮች የካፒታሊዝም ሥርዐት እስከሠፈነ ድረስ፤ ያ የተሣካው አብዮት ባለቤት የሆነው ሀገር በካፒታሊዝም ከበባ መጥፋት ካልፈለገ በቀር በሁሉም መንገድ መንግሥቱን፤ የመንግሥቱን አካሎች፤ የስለላ ክፍሉን፤ ጦሩን ማዳከም ሣይሆን ማጠናከር እንዳለበት ገልጸዋል። የሩስያ ማርክሳውያን የኤንግልስ ሀሣብ ኅብረተሰባዊ አብዮት በሁሉም ወይም ባብዛኛኖቹ አገሮች ድል ባገኘበት ጊዜ ሊሠራ የሚችል እንደሆነና ኅብረተሰባዊነት ባንድ ሀገር ብቻ ድል ባገኘበትና በተቀሩት ሀገሮች ካፒታሊዝም በሰፈነበት ቦታና ጊዜ ላለ ሁኔታ እንደማይሠራ ተገንዝበዋል። እነሆም ኅብረተሰባዊ መንግሥትን በሚመለከት ረገድ ሁለት የተለያዩ፤ አንዳቸው ሌላቸውን የሚገፉ ሀሣቦችን እናገኛለን። መጽሐፋውያንና ቀኖናውያን ይህ ዓይነት አተያይ ከባድ ችግር እንደሚፈጥርና አንደኛው ቅርጸ ሀሣብ ፍጹም ስሕተት ተብሎ መተው እንዳለበት፤ ሌላኛውና ፍጹም ትክክል ነው የሚሉት በኅብረተሰባዊ መንግሥት የእድገት ዘመናት በሙሉ በሥራ ላይ ሊውል የሚገባ መሆኑን ይናገራሉ። ማርክሣውያን ግን መጽሐፋውያኑና ቀኖናውያኑ እንደተሣሣቱና፤ ሁለቱም ሀሣቦች ፍጹም ሣይሆኑ ለየራሣቸው ጊዜ ትክክል እንደሆኑ ያውቃሉ። የሶቭዬት ማርክሣውያኑ ሀሣብ ኅብረተሰባዊነት ባንድ ወይም በብዙ ሀገሮች ድል ባገኘበት ጊዜ ይሠራል። የኤንግልስ ሀሣብ የሚሠራው በተለያዩ ሀገሮች የሚገኙት የኅብረተሰባዊነት ተከታታይ ድሎች ወደ አብዛኞቹ ሀገሮች ኅብረተሰባዊነት ድሎች በሚያመሩበት ጊዜና የኤንግልስን ሀሣብ በተግባር ላይ ለማዋል አስፈላጊዎቹ ሁኔታዎች በሚፈጠሩበት ጊዜ ነው።

ጓድ ኮሎፖቭ ከተለያዩ የእስታሊን ሥራዎች ውስጥ በደብዳቤዎ ስለ ጠቀሣቸው በቋንቋ ጉዳይ ላይ ስለ ተሠጡ ሁለት ሀሣቦች ይህንኑ ማለት ይቻላል።

ጓድ ኮሎፖቭ ከተለያዩ የእስታሊን ሥራዎች ውስጥ በደብዳቤው ስለጠቀሣቸው በቋንቋ ጉዳይ ላይ ስለ ተሰጡ ሁለት ሀሣቦች ይህንኑ ማለት ይቻላል።

ስታሊን «በሥነ ቋንቋ ውስጥ ማርክሲዝምን ስለሚመለከተው» በሚለው ጽሑፉ «በሁለት ቋንቋዎች መዳቀል ጊዜ አንደኛው ሲሞት ሌላኛው ድል አድርጐ ይወጣል። በዚህም ምክንያት መዳቀል ሌላ አዲስ ሶስተኛ ቋንቋ አይፈጥርም፤ አንዱን ቋንቋ አጽንቶ ያቆያል እንጂ፤ ...» ያለውን ጓድ ኮሎፖቭ ይጠቅሰዋል። በተጨማሪም በሶቭዬት ኅብረት የኮሚኒስት ፓርቲ አስራ ስድስተኛ ሰብሰባ ላይ እስታሊን» በዓለም በመላ የኅብረተሰባዊነት አብዮት ድል በሚገኝበት ዘመን፤ ኅብረተሰባዊነት ተጠናክሮ የየዕለት ሕይወት አካል ሲሆን ብሔራዊ ቋንቋዎች በእርግጥ

አንድ ቋንቋ ይሆናሉ፤ ይህም አንድ ቋንቋ ሩስይኛ ወይም ጀርመንኛ ሣይሆን አዲስ ቋንቋ ነው» ያለውን ይጠቅሣል። እኒህን ሁለት ሀሣቦች በማወዳደር እርስ በርሣቸው የተሸራረቡ ነገሮች ሣይሆኑ አንዳቸው አንዳቸውን የሚጋፉ አድርጐ በመገመት ጓድ ኮሎፖብ ተስፋ በመቁረጥ የደረሰ ይመስላል። «ከጽሑፍዎ» ሲል ይጽፋል በደብዳቤው «የቋንቋዎች መዳቀል አንድ አዲስ ቋንቋን ከቶም ሊፈጥር አይችልም እንደሚል ነበር የገባልኝ፤ ከጽሑፍዎ በፊት ግን በሶቭዬት ኅብረት የኮሚኒስት ፓርቲ አስራ ስድስተኛ ስብሰባ ላይ ባደረጉት ንግግር በኮሙኒዝም ቋንቋዎች ተዛንቀው አንድ ቋንቋ ይሆናሉ ማለቶን ተገንዝቤ ነበር።»

ጓድ ኮሎፖብ በኒህ ሁለት ሀሣቦች ውስጥ ቅራኔዎች በማየት ቅራኔዎቹም መወገድ እንዳለባቸው በማመን አንደኛውን ሀሣብ ትክክል እንዳልሆነ አይቶ መተውና ሌላኛውን ለሁሉም ጊዜና ቦታ እንደሚያገለግል ትክክል ሀሣብ መቀበሉ የሚያስፈልግ መስሎታል፤ የትኛውን ሀሣብ መምረጥ እንዳለበት ግን አላወቀም። ውጤቱ ተስፋ የሚያስቆርጥ ነገር ነው የሚሆን። ጓድ ኮሎፖብ እያንዳንዱ ሀሣብ ለየራሱ ጊዜ ትክክል እንደሚሆን እንኳን አልጠረጠረም። ይህ ዓይነቱ ችግር የነገሮችን አላባ የማይመረምሩ፤ ዝም ብለው ጥቅሶቹ ከሚያወሩት የታሪክ ሁኔታዎች ገንጥለው የሚዘርፉና ተስፋ በሚያስቆርጥ ሁኔታ ላይ የሚገኙ የመጽሐፋውያንና የቀኖናውያን ችግር ነው። ይሁንና የነገሩ አላባ ለሚመረምር ሁኔታው ተስፋ የሚያስቆርጥ ነው ለማለት ምክንያት አይኖረውም። ዋናው ነገር «በሥነ ቋንቋ ውስጥ ማርክሲዝምን ስለሚከተለው» የሚለው የስታሊን ጽሑፍና በአስራ ስድስተኛው ፓርቲ ስብሰባ ላይ ያደረገው ንግግር የተለያዩ ዘመናትን ነበር የሚጠቅሱ። በዚህም ምክንያት ሁለቱ ሀሣቦች የተለያዩ ናቸው።

እስታሊን በጽሑፉ ውስጥ ስለ ቋንቋዎች መዳቀል ያቀረበው ሀሣብ የሚጠቅሰው - በዝባዥ መደቦች በዓለም ሠፋኝ ሀይሎች የሆኑበትን፤ ብሔራዊና የቅኝ አገዛዝ ጭቆና ያሉበትን፤ ብሔራዊ ግንጥልነትና በብሔሮች መሀል ያለ ያለ መተማመን በመንግሥታት መሀል ባለ ልዩነት የተጠናከረበትን፤ ብሔራዊ የእኩልነት መብቶች ገና ያልጸደቁበትን፤ የቋንቋዎች መዳቀል ከቋንቋዎቹ ለአንዱ የበላይነትን ለማስገኘት የሚደረግ ትግል የሆነበትን፤ ለብሔሮችና ለቋንቋዎች ሰላማዊና ውጤታዉ ትብብር አስፈላጊ የሆኑት ሁኔታዎች ገና ያለመለሙበትን፤ የጊዜው ተቀዳሚ ነገር የቋንቋዎች መዋሃድና የሌሎች ድል ማግኘት የሆነበትን፤ - የኅብረተሰባዊነት ድል ገና በመላው ዓለም ያልሰፈነበትን ዘመን ነው። በዚህ ዐይነት ሁኔታዎች ሊኖሩ የሚችሉ አንድም ድል ያደረጉ አንድም ድል የተደረጉ ቋንቋዎች ብቻ መሆናቸው ግልጽ ነው። የሁለት ቋንቋዎች መዳቀል የአዲስ ቋንቋ መፈጠርን ውጤት አያስገኝም፤ ከሁለቱ ቋንቋዎች ያንዳቸውን ድል ማድረግ የሌላኛውን ድል መሆን እንጂ፤ - ሲል እስታሊን የጻፈው የተባሉትን ሁኔታዎች ተመልክቶ ነው።

እስታሊን በአስራ ስድስተኛው የፓርቲ ስብሰባ ላይ ባደረገው ንግግር በተለይም ስለ ቋንቋዎች መዛነቅና አንድ የጋራ ቋንቋ መሆን ባተተበት ጊዜ የጠቀሰው፤ የተለየ ዘመንን ነበር። ይህም ዓለም ዓቀፍ ኢምፔሪያሊዝም የጠፋበትን፤ በዝባዥ መደቦች ድል የመቱበትንና የብሔርና የቅኝ አገዛዝ ጫና የተወገደበትን፤ ብሔራዊ ግንጥልነትና በብሔሮች መሀል ያለው ያለ መተማመን በጋራ እምነትና በብሔሮች መሀል በተመሠረተ መቀራረብ የተተካበትን፤ ብሔራዊ

እኩልነት ቢገበር የተገለጸበትን፤ ቋንቋዎችን ጨቁኖና ደቁሶ የማዋሀድ ፖሊሲ የቀረበትን፤ የብሔሮች ትብብር የደረጀበትንና ብሔራዊ ቋንቋዎች በርስ በርስ ትብብር በነጻ መንገድ አንዳቸው ሌላቸውን ሊያበለጽጉ የቻሉበትን፤ - በዓለም ሁሉ ኅብረተሰባዊ ድል ከገኘ በኂላ ያለን ዘመን ነው። በዚህ ዘመን ያንዳንድ ቋንቋዎች ድል ማድረግ የሌሎች ቋንቋዎች ድል መሆን ብሎ አይኖርም። በዚህ ዘመን አንዱ ተሸናፊ ሌላው አሸናፊ የሁኑ ሁለት ቋንቋዎች አይኖሩም። ይልቅስ በመቶ በሚቆጠሩ ብሔራዊ ቋንቋዎች ውስጥ በብሔሮች መሀል በሚደረግ የረዥም ጊዜ ኢኮኖሚያዊ ፖለቲካዊና ባህላዊ ትብብር በመጀመሪያ እጅግ የበለጸጉ ከብዙ ብሔሮች ቋንቋዎች ውህደት የተገኙ ቋንቋዎች በየቀጠናው መገኘት ይጀምራሉ። ቀጥሎም እኒህ የቀጠና ቋንቋዎች ወደ አንድ ዓለም አቀፋዊ ቋንቋ ይለወጣሉ። ይህ አንድ ቋንቋ ጀርመንኛ፤ ሩስይኛ ወይም እንግሊዝኛ ያልሆነ፤ ግን ከብሔሮች ከቀጠና ቋንቋዎች ምርጥ ምርጥ ነገሮችን የያዘ አዲስ ቋንቋ ይሆናል።

ስለሆነም፤ ሁለቱ የተለያዩ ሀሣቦች በማኅበረሰብ የዕድገት ታሪክ ውስጥ ያሉ ሁለት የተለያዩ ዘመናትን ነው የሚጠቅሱ። በዚህም ምክንያት ሁለቱም ሀሣቦች ለየዘመናቸው ትክክል ናቸው። እኒህ ሁለት ሀሣቦች አይለያዩም ማለት፤ አንዳቸው አንዳቸውን አይግፉ ማለት፤ የካፒታሊዝም የበላይነት ዘመን ከኅብረተሰባዊነት የበላይነት ዘመን አይለይ፤ ኅብረተሰባዊነትና ካፒታሊዝም አንዳቸው አንዳቸውን አይግፉ እንደ ማለት ያለ ግራ ቢስ የሆነ ሀሣብ ነው።

መጽሐፋውያንና ቀኖናውያን ማርክሲዝምንና የማርክሲዝምን ልዩ ልዩ የማሰሪያ ሀሣቦችንና ቅርጸ ሀሣቦችን የማኅበረሰብ ዕድገት ሁኔታዎች ቢለውጡም እንኳን እነሱ «ምን ጊዜም» እንደማይለወጡ አድርገው ይቆጥሯቸዋል። ማሰሪያ ሀሣቦቹና ቅርጸ ሀሣቦቹ ለምንም የሕይወት ጉዳይ፤ ዘመንና ሥፍራን ሣይለዩ እንደሚያገለግሏቸው በመቁጠር እኒህን ማሰሪያ ሀሣቦችና ቅርጸ ሀሣቦች በቃላቸው ሸምድደው እንዳጋጠመ መጥቀስ ከቻሉ ምንም ችግር ሊፈቱ የሚችሉ ይመስላቸዋል። ግን እንዲህ ዐይነቱ አስተሳሰብ የማርክሲዝምን ሀሁ ገና የቆጠሩ እንጂ ፍሬ ነገሩን ያልጠነቀቁ በቃላቸው የማሰርያ ሐሳቦችንና የማርክሲዝምን ቅርጸ ሀሣቦች የሸመደዱ ግን ትርጉሙ ያልገባቸው ሰዎች አስተሳሰብ ነው።

ማርክሲዝም ተፈጥሮንና ማኅበረሰብን የሚገዙ ሕግጋት ሣይንስ ነው። የተጨቆኑና የተበዘበዙ መደቦች ሣይንስ ነው። በሁሉም ሀገሮች የኅብረተሰባዊ ድል የሚገኝበት ሣይንስ ነው። የኮሚኒስት ማኅበረሰብ የሚገነባበት ሳይንስ ነው። ሳይንስ እንደ መሆኑም ባንድ ረግቶ አይቆምም፣ እያደገና ምላት እያገኘ እንጂ። በእድገቱም በአዲስ ልምድ በአዲስ ዕውቀት እየበለጸገ ይሄዳል። በመሆኑም አንዳንድ ቅርጸ ሀሳቦቹና ማሰሪያ ሀሣቦቹ እያደር ለአዲሱ ታሪካዊ ተግባር በሚስማሙ ቅርጸ ሀሣቦችና ማሰሪያ ሀሣቦች ይተካሉ። ማርክሲዝም ለሁሉም ዘመን ለሁሉም ሥፍራ የሚሆኑ የማይለወጡ ማሠሪያ ሀሣቦችና ቅርጸ ሀሳቦች የሉትም። ማርክሲዝም የምንም ዐይነት ቀኖናዊነት ጠላት ነው።

ሐምሌ 28 1950

ፕራቭዳ፤ ነሐሴ 2 1950

## አምደ ቃላት

### ማኅበረሰብ - Spciety

የተለመደውን «ኅብረተሰብ» የሚለውን ቃል «የሰዎች ዕድር» በሚለው ትርጉሙ) በመተካት ነው የተጠቀምኩበት። ዛሬ ኅብረተሰብ ከሚለው ቃል የወጣው ቅጽል ኅብረተሰባዊ ከካፒታሊስት ሥርዓት ቀጥሎ ያለው ሥርዓት ስያሜ በመሆኑ፤ ከዚሁ ቃል ነባር ትርጉም ጋር አልፎ አልፎ መጋጨትና አሻሚ መሆኑ አልቀረም። ለምሳሌ ኅብረተሰባዊ ክስተት ብንል የኅብረተሰቡ (የሰዎች ዕድር) ክስተት ወይም የኅብረተሰባዊ የሶሻሊስት ሥርዐት) ክስተት ማለታችን እንደሁ ግልጽ አይደለም። ይህን ችግር ለማቃለል ስሞክር፤ ኅብረተሰብ- የሰዎች የሚል ቃል (ብዙም ባይሠራበት) መኖሩ ታሰበኝና በዚሁ ቃል እስከመጨረሻው ግን ሥርዐቱን በሚመለከት ረገድ ብቻ እንዲውል አድርጌ ተገለገልኩበት።

መድበለ ቃላት - Vocabulary

ባንድ ቋንቋ ውስጥ ያለ የቃላት ክምችት

ሥነ ቋንቋ - Linguustics

የቋንቋ ሣይንስ፤ - የቋንቋ ባህርይ የሚመረመርበት የትምህርት ዘርፍ

ሥነ ይዘተ ሀሣብ - Semantics

ቅርጸ - ሀሣብ - Formula

ኢኮኖሚያዊ መዋቅር - Basis

በዚህ ቃል (ሐረግ) መገልገሌን ትቼ ተራማጅ መዝገበ ቃላት በሰጠው «መሠረት» በሚለው ቃል መጠቀም እችል ነበር። ይሁንና በዚህ «አዲስ» ቃል መጠቀሜ አንደኛ ይህ ቃል በተራ ከተለመደው መሠረት (በመሠረቱ እንዲሉ) ከሚለው ቃል ጋር መጋፋቱንና የትርጉም መሻማት ማስከተሉን በማየቴና ይህንም አሻሚነት በአማርኛ አንባቢዎች ዘንድ ቅርጹ ከቆመለት ጽንስ ሃሣብ አለመለመድ ጋር ሳነጻጽረው በዐውደ ንባቡም (በኮንቴክስቱም) እንኳን ቢሆን ማስወገድ ይቻል ስላልመሰለኝ፤ ሁለተኛም ይህ ጽንሰ ሐሳብ በቅርጹ አብሮት ከሚቋጨው ሉዓላዊ (ላዕላይ) ከሚለው ጽንሰ ሐሳብ ቅርጽ ጋር እንዲሰምር በመፈለጌ ነው።

የቋንቋ ዘዬ - Dialect

ይህ የአካባቢን ወይም የሥፍራን የቋንቋ መልክ ብቻ ሣይሆን ሌሎችንም በተለያዩ ሁኔታዎች ውስጥ የሚያጋጥሙን ልዩ ልዩ የቋንቋ መልኮች ያጠቃልላል።

የንዳ ቋንቋ - Jargon

የተወሰነ ቡድን የሚጠቀምባቸው አብዛኛውን ጊዜ ከሥራው ጋር የተያያዙ የቋንቋ ፈሊጦች።

## ማስታወሻዎች።

1. «ማርክሲዝምና የቋንቋ ችግሮች -» የሚለው የእስታሊን ጽሑፍ በፕራቭዳ ላይ የታተመው ሰኔ 20 ቀን 1950 ዓ.ም ነበር። ከዚህ በፊት በፕራቭዳ ላይ በሶቭዬት የሥነ ቋንቋ ችግሮች ላይ ውይይት ተደርጎ ነበር። ይህ የጓድ ስታሊን ጽሑፍ በውይይት ሣቢያ የሶቭዬት ተማሪዎች ላቀረቡለት ጥያቄዎችና በፕራቭዳ ዓምዶች ላይ ለውጡት ጽሑፎች መልስ ነው። የጽሑፎቹ አርእስት «በቁሣዊ ሥነ ቋንቋ ጥርጊያ ላይ» - በዩክራንያ የሣይንስ አካዳሚ አባል በቡላኮቭስኪ፤ «የማር መላምትና የሩስያ ሥነ ቋንቋ ታሪክ» - በኒኪፎሮቭ፤ «በቋንቋ የመደብ ጠባይ ችግር ላይ» በኩድሽለተቭና ሌሎችም ነበሩ።
2. ካርልማርክስና ፍሬድሪክ ኤንግልስ፤ ሥራዎች፤ ጀርመንኛ፤ እትም፤ በርሊን 1958 ቅጽ 3 ገጽ 212
3. ዝኒ ከማሁ ገጽ 411-12
4. ዝኒ ከማሁ፤ 1975 ቅጽ 3 ገጽ 351
5. ፖል ልፋርግ 1842-1911 የታወቀ የፈረንሣይ የዓለም ዓቀፍ የሠራተኞች እንቅስቃሴ ንቁ ታጋይና ማርክሳዊ ታላቅ የፕሮፓጋንዳ ምሁር። ከፈረንሣይ የሠራተኞች ፓርቲ መሥራቾች አንዱ። የማርክስና የኤንግልስ ተማሪና ጓድ ከመሆኑ ጋር የማርክስን ልጅ ሎራን አግብቶ ነበር።
6. ባንድ፤ የሎታንያ የፖላንድ የሩስያ አጠቃላይ የይሁዳውያን ሠራተኞች አንድነት፤ በቪልና በጥቅምት 1897 በተደረገው ስብሰባ ላይ የተቋቋመ በይሁዳውያን የእጅ ሥራ ባለሙያዎች መሐል ባብዛኛው ይሠራ የነበረ ይሁዲ የንዑስ ከበርቴ ወላዋይ ድርጅት ነው። በ1898 በተደረገው የሩስያ ሶሻል ዲሞክራቲክ የሠራተኞች ፓርቲ የመጀመሪያ ስብሰባ፤ ባንድ «የይሁዳውያን ወዝ አደሮችን  ልዩ ልዩ ችግሮች ብቻ የሚመለከት ነጻ ራሱን የቻለ ድርጅት» በመሆን ፓርቲውን ተደባለቀ። በፓርቲው ውስጥ አንዴ ከገባ በኋላ ግን በሩስያ የሠራተኛ መደብ እንቅስቃሴ ውስጥ የብሔረተኝነትንና የመገንጠልን ሀሣቦች ያስፋፋ ጀመር። በዚህም ሌሊን ከመሠረተው አስከራ ከሚባለው ጋዜጣ ባንዳዊው የከበርቴ ብሔረተኝነት አቋም ከፍ ያለ ቅዋሜ ደረሰበት።
   ቪ. አይ ሌኒን፤ «የራስን ዕድል በራስ የመወሰን የብሔሮች መብት» ምርጥ ሥራዎች በሁለት ቅጾች፤ እንግሊዞች እትም፤ ሞስኮ፤ 1952 ቅጽ 1 ክፍል 2 ገጽ 318-9
   ጄ.ቪ. እስታሊን፤ «የብሔር ጥያቄና ሌኒንዝም» ሥራዎች፤ እንግሊዝኛ እትም፤ ሞስኮ፤ 1945 ቅጽ 2 ገጽ 353
   ኤን ዋይ ማር 1864-1934 የሩስያ የቋንቋ ምሁር። ይህ የቋንቋ ምሁር ቋንቋ በኢኮኖሚያዊ መዋቅሩ ላይ ያለ የሉዓላዊ መዋቅሩ ክፍል ነው ይል ነበር። በዚህና በሌሎችም በቋንቋ ላይ ባሉት የተሣሣቱ አስተሳሰቦች ምክንያት በየጊዜው ከጆሴፍ እስታሊን ብርቱ የሂስ በትር ተሠንዝሮበታል።

የአራት ነገር ትንተና - የማር የሰው ልጅ የጥንት ቋንቋ አነጋገር ከአራት ቀለማት፣ ሳል፣ በር፣ ዬን፣ ሮሽ ከሚባሉት የወጣ ነው ይላል።

«የቋንቋ ነቅዐ - ዘር» መላ ምት፣ - ቤተሰብ ቋንቋዎች ከወል የጥንት «አባት ቋንቋ» የተከፈለ የቋንቋ ዘዬዎች ይዘዋል የሚል የሕንዲ አውሮፓዊው ትምህርት ቤት መምላት ነው። ለምሣሌ፣ ዘመናዊው ኢጣልያንኛ፣ ፈረንሣይኛ፣ እስፔንኛ፣ ፓርቱጋልኛ፣ ሮማንኛ ከላቲን የወጡ እህትማማች ቋንቋዎች ናቸው፣ ጥንትም የተለያዩ የቋንቋዎቹን «አባት ቋንቋ» መኖር የሚያረጋግጡ የጽሑፍ ማስረጃዎች ባለመኖራቸው የሕንዲ አውሮፓውያኑ ሊቃውንት መላምታዊ «አባት ቋንቋ» አወጡ። ዋናው ዓላማቸው የድምጽ ሕግጋትን ገለጸ ማቃናት ነበር። ዳሩ ግን የእውነትነቱ መጠን ለማረጋገጥ ምንም መንገድ የለም።

12. ካርል ማርክስና ፍሬድሪክ ኤንግልስ፣ *ሥራዎች*፣ ጀርመንኛ እትም፣ በርሊን፣ 1958 ቅጽ 3 ገጽ 430 እና 432